# መግቢያ

በዚህ፡ ትንሽ፡ መድበል፡ ውስጥ፡ የሠፈሩት፡ ግጥሞች፡ ከ፲፱፻፷ ዓ.ም. ጀምሮ፡ በተለያየ፡ ጊዜ፡ የተገጠሙ፡ ናቸው። ከነዚህ ውስጥ፡ ጥቂቶቹ፡ ከተወለዱ፡ በኋላ፡ ታርቀዋል፤ ተቀጥተዋል። እንዳንዶቹ፡ ደግሞ፡ እፍታዊ፡ ግጤት፤ አለያም፡ ያንድ፡ እፍታ፡ ተመስጦ (ኢንስፒሬሽን) እንዳፈለቃቸው፡ የተተዉ፡ ናቸው። ይህ፡ ስለተገለ፡ ግን፡ ለቅዱስ፡ ያሬድ፡ የዜማ፡ ሥልቶቹን፡ ያፈለቁለት፡ አዕዋፍ፡ ከእኔ፡ ጋር፡ መኅበር፡ ውለው፤ ወይም፡ በነሱ፡ የተመሰለው፡ መለኮታዊ፡ ኪን፡ በኔም፡ አድሮ፡ በደመ፡ነፍስ፡ ያናገረኝ፡ ቃላት፡ ናቸው፡ ማለት፡ አይደለም። በሰሎሞን፡ ዴሬሣ፡ የ"ልጅነት"፡ ቋንቋ፡ እምቢ፡ ባለው፡ ፈንቅለው፡ የወጡ፡ ናቸው። "የስሜት፡ ንፃሬዎች" በሚል፡ አጠቃላይ፡ ርእስ፡ ሥር፡ ያለአርእስት፡ የቀረቡት፡ ግጥሞች፡ የዚህ፡ እፍታዊ፡ ግጤት፡ ምሳሌ፡ ሆነው፡ ሊታዩ፡ ይችላሉ። ለሁሉም፡ ቢሆን፡ ግን፡ ለግጤቱ፡ ምክንያት፡ የሆኑት፡ ነገሮች፤ ሁኔታዎች፤ ወይም፡ ሀሳቦች፡ ከዚሁ፡ ካለንበት፡ ምድር፡ ያሉ፡ ናቸው። እፍታዊነታቸው፡ በአእምሮ፡ ተፀንሰው፡ ከሃዕር፡ የፈለቁበትንና፡ ከወረቀት፡ መልክ፡ የያዙበትን፤ ሥጋ፡ የለበሱበትን፤ አንደበት፡ የገዙበትን፡ ሁኔታና፡ ፍጥነት፡ የሚያመለክት፡ ነው። እንዳንዶቹ፤ በተለይ፡ ግን፡ "ያንድ፡ አዝማሪ፡ ዘፈን"፡ እና፡ "አዲስ፡ ግጥም"፤ ይሁነኝ፡ ተብሎ፡ ለሙከራ፡ ያህል፡ ከተነደፉ፡ በኋላ፡ የታረሙ፡ ናቸው፡ — ያመረቃሉ፡ አያመረቁም፡ የሚለውን ለአንባቢ፡ እንደ፡ እተዋለሁ።

ለመሆኑ፡ ግጥሞቹ፡ ስለምንድን፡ ናቸው፡ የሚል፡ ጥያቄ፡ (በተለይ፡ ስለእንደ፡ ሁለቱ) መነሣቱ፡ አይቀርም። ብየ፡ ልገምትና፡ "እንብባችሁ፡ ደረሱበት" ብየ፡ ብመልስ፡ ቅር፡ አትሰኙ፡ አደራ! ጥያቄውን፡ ማቃለል፤ ወይም፡ ሊመለስ፡ የማይችል፡ ጥያቄን፡ በብልጣ—ብልጥነት፡ ባቋራጩ፡ ለማምለጥ፡ የተደረገ፤ ወይም፡ የምሁራዊ፡ ንቀት ወይም፡ ትዕቢት፡ ጉዳይ፡ አይደለም። ተገቢው፡ መልስ፡ ይኸው፡ ብቻ ስለሆነ፡ ነው — ቢያንስ፡ በዚህ፡ ሁኔታ! የዚህ፤ በእርግጥም፡ እንደየሁኔታው፡ ተገቢነት፡ ያለው፡ ጥያቄ፡ መልስ፡ ከግጥሞቹ፡ ከራሳቸው፡ ብሎም፡ ከአንባቢ (አንባቢ፡ ካገኙ) የትርጓሜ፡ ዓይነት፡ ተፈልፍሎ፡ ይገኛ፡ ዘንድ፡ የግጥም፡ ጥበብ (ባጠቃላይም፡ የሥነ፡ ፅሑፍ፡ ጥበብ) ግድ፡ የሚለው፡ ነገር፡ ነው።

ግጥሞቹን፡ አንብቦ፡ ትርጓሜ፡ የመስጠቱ፡ ነገር፡ ቁም፡ ነገር፡ እንዳለው፡ ጨዋታ፡ ነው። ሽምብራ፡ ጠርጥሮ፤ ባቄላ፡ ፈልፍሎ፡ መብላት፡ እርካታው፡ እሁለቱ፡ ላይ፡ ነው — እንደም፡ በልቶ፡ ረሀብን፡ ማስታገሱ፡ ወይም፡ መጥገቡ፡ አለ፤ እንደም፡ መፈልፈሉ፡ ጥበብን፡ የሚጠይቅ፡ ጨዋታ፡ መምሰሉ፡ ነው። በግጥሞቹ፡ ውስጥ፡ ሊኖር፡ የሚችለውን፡ ትርጉም፡ ፈልፍሎም፡ ይሁን፡ ጠርጥሮ፡ ማውጣቱ፤ የተገኘውንም፡ ፍሬ ነገር፡ አላምጦ፡ ማጣጣሙ፡ — ማለትም፤ ጥያቄውን፡ አንሥቶ፡ ለመመለስ፡ አስተዋፅኦ፡ ማድረጉ — የአንባቢ፡ ፈንታ፡ ነው። ይህ፡ እኔንም፡ ይጨምራል፤ ምነው፡ ቢሉ፡ ግጥሞቹን፡ አሁን፡ የማይበት፡ እንፃር፡ ሊፀነሱና፡ ሊፃፉ፡ ከነበርኩበት፡ እንፃር፡ ትንሽም፡ ቢሆን፡ የተለየ፡ ነውና። እና፡ ሁሉም፡ እንደ፡ ብሶቱ፤ እንደ፡ ክሒሎቱ፡ ያደርጋቸው፡ ዘንድ፡ ነፃ፡ ነው።

ይህ፡ ስለተባለ፡ ግን፡ ሁሉም፡ እንዳሻው፤ የፈለገውን፡ እየከተተ፡ ነገሩን፡ መልክ፡ ያለመልኩ፡ እያሳቆጠ፡ ጠቅልሎ፡ ይዋጠው፡ ማለት፡ አይ

ዲሰም። ከግጥሞቹ፡ ይዞታ፣ ከቃላቱ፡ አሰካክና፡ አገባብ፡ ውጭ፡ ትርጉም መጨመር፡ ነገሩን፡ መደረት፡ ይሆናል። አንድም፣ አንዲት፡ ቃል፡ ነጥሎ፡ በዓለም፡ ላይ፡ ሊኖራት፡ የሚችለውን፡ ትርጉም፡ እያሸተቱ፡ ለማስተንተን፡ መሞከሩ፡ የቋንጫ፡ መሳሳጫ፡ ማውጣት (ወይም፡ "ፀጉር፡ መሰንጠቅ፡") ይሆንና፡ አንባቢና፡ ግጥም፡ ተለያይተው፡ ይቀራሉ። የአንባቢ፣ የተርጓሚ፡ ነፃነት፡ በግጥሞቹ፡ ክበብ፡ የተገደበ፡ ነው። የቃላት፡ አገባብ፣ የሐረግ፡ አሰካክ፣ የስንኞች፡ ቅደም፡ ተከተል፣ ይህና፡ ሌላ፡ ሌላም፡ የግጥም፡ ሥልት፡ ለምንሰጠው፡ ትርጓሜ፡ ፍንጭ፡ ሰጪ፡ ወይም፡ ፋና፡ ጉብሪ፡ ሊሆን፡ ይችላል።

በግጥም፡ ዓለም፡ ምላጭ፡ ሲያብጥ፡ ውሃ፡ ሲያንቅ፡ ሰምተን፡ እናውቃለን። በግጥም፡ ዓለም፡ ፍየል፡ ዐይኗን፡ ሲያማት፡ ነገር፡ እንጂ፡ ነው፡ ጌሉ፡ የሚያከማት። በዚህ፡ ልዩ፡ ዓለም፡ ደንጊያ፡ ደም፡ አልቅሶ፡ ውሾ፡ እሱን፡ ልሶ፡ ሲሞት፡ እናያለን። በዚህ፡ በምናውቀው፡ እንግዳ፡ ዓለም፡ የተፈጥሮ፡ አካሄድ፡

... ፍጥነቱ፣ እንደዔሊ፡ ሲወረወር
አንድ፡ [እግሩ]፡ ተነሥቶ፡ እስኪያርፍ፡
ያልፋሉ፡ ሺህ፡ ዘመናት*

በዚች፡ መድበል፡ ውስጥም፡ አምሳክን፡ ሰድቦ፡ ማስለቀስ፡ ታገኙታላችሁ፤ በጊዜ፡ ላይ፡ ተፋቶ፡ የሚሆነውን፡ ታያላችሁ፤ ከመሬት፡ ቂጣ፡ ቀጥቅጦ፣ ከውሀ፡ ቅቤ፡ ንጦ፡ አቅልጦ፡ መርካትን፡ ትታደሳላችሁ። ገጣሚው፣ ቃላት፡ ልዩ፡ ኃይል፡ አላቸው። የዘወትሩን፡ እንግዳ፣ አሮጌውን፡ አዲስ፡ ያደርጋሉ። የተበታተነውን፡ ይሰበስባሉ፤ አጥንቱን፡ ሥጋ፡ ያለብሳሉ፤ በበድኑ፡ የሞቀ፡ እስትንፋስ፡ ለቀው፡ ነፍስ፡ ይዘራሉ። እንደሁኔታው፣ ዘለዓለማዊ፡

---

* ከበደ፡ ካሣ፣ "ተፈጥሮ"፡ በሚል፡ ግጥሙ፡ ካሠፈራቸው፡ መሥመሮች፡ የተጠቀሰ።

ህይወትን፡ ይሰጣሉ፤ ወይም፡ እመቀመቅ፡ ያወርዳሉ። በሠነ፡ ፅሑፍ፣
ዓለም፡ ቃላት፡ ሁሉን፡ ቻይ፤ ሁሉን፡ አድራጊ፡ ናቸው። በዚህ፡ ልዩ፡ ዓለ
ም፡ ኋላፊና፡ ኣሚጋው፡ እነሱው፡ እንጂ፡ ናቸው — ሁሉም፡ ሲያልፉ፣
የሚቀሩ!

የመጀመሪያ፡ ትምህርታችን፡ ከዚህ፡ ላይ፡ ሆኖ፡ ሌላውን፡ ሁሉ፡ ከ
ዚህ፡ ጋር፡ ከያይዘን፡ እንመልከተው። በተረፈ፡ ይህችን፡ ትሑት፡ የፅ
ሑፍ፡ መድበል፡ አንባቢ፡ የመውደድም፡ ሆነ፡ የመጥላት፡ ጉዳይ፡ የየግ
ላችን፡ ሲሆን (ከያኔ፡ የማልሰጥበት፡ ነገር፡ ነውና)፤ ከቻ፤ ወደፊቱም፡ የ
ምኞ፡ ፍቅር፤ ኝነቻውም፡ የእልህ፡ እንዳይሆን፡ አደራ!

የ.ኤ

ሎስ፡ አንጀለስ

## የአዋቂ፡ጥያቄ

በዝምታ፡ከንፈር፡መጦ — ወይ፡በጩኸት፡ዐይን፡አፍጥጦ፤
ችላ፡ማለት፣መታባቱ — ወይ፡ተናጁ፡መደገፉቱ፤
ግራን፡መስጠት፡ቀኝ፡ሲመታ፣
ወይ፡አፀፋውን፡መመለስ፡እንዳፍታ፤
መታነቁ፣ወይ፡ማነቁ፣
ወይም፣ነገርን፡መተው፡መናቁ፤
መለዘቡ — መሻከሩ፣
መቨርበሩ፣ወይም፡ደግሞ፡መበርበሩ፤
በንፉግ፡ዘንድ፡መባዘቱ — ወይም፣ሲያጡ፡ገድሎ፡መሞቱ
ለጦር፡ሂዱ፡መዋጋቱ፣ወይ፡መሸሹ፤
ንፁህ፡መስሎ፡መታየቱ፣መቆሸሹ፤
ቀኑ፡ሲመሽ፣ነጋ፡ጠባ፣
ምርጫው፡ሁሉ፣በየፈርጁ፡ካልቀረበ፡ካልተጠና፣
ህልውና፡ምን፡ሊፀና!

●

## ያላዋቂ፡መልስ

አይ፡ወዳጄ!
ቢከፉህ፣ዝም፡ብለህ — አፍህን፡ተለጉመህ፣
ቀኝ፡ቢሉህ፣ግራ፡መልሰህ — አንድ፡ሁለት፡ጥሬ፡ተልሰህ፤
ብርዝ፡ሲወጣህ፡ስጣፍጥ — ሰፈፍ፡ወጥቶልህ፡ስትቀልጥ፣
ሰም፡ተጨፍልቀህ፡ስትጧፍ፣
ይተክሉህና፡ከመቅረዝ፣

ይለኩሱሃል፡ ያበሩሃል፤

በፋናህ፡ ዞሬያ፡ ከበሮ፡ ይዱልቁልሃል።

ታፀድቃለህ፡ ታማልድ!

ከዚህ፡ ኑሮ፡ ምን፡ ሊገድ!

አየህ!

እገል፡ ብለህ፡ ስትሄድ — ደየ፡ ቢጠቀም፡ ከመንገድ፣

ንስሐ፡ ገብተህ፣ ማረኝ፡ ብለህ፣

ማቅህን፡ ለብሰህ፡ ዐመድ፡ ቅመህ፣

እንድትመስል፡ እህዮን፣

በግብር፡ ወንድምህን።

ታፀድቅ፡ እንጂ፡ ታማልድ!

ታፀድቅ፡ እንጂ፡ ታማልድ!

ከዚህ፡ ኑሮ፡ ምን፡ ሊገድ!

፲፱፻፷፫ ዓ.ም.



## ተናጋሪ፡ጠፍቶ?

### (ወይም፣ የሥጋ፡ጥያቄ)

መችː ጨነቀኝና፡የናንተ፡ልፍለፋ፣
በናንተ፡ልፍለፋ፡
ንብረቴ፡ሳይፋፋ።
ትዳሬስ፡ካልሞላ፡ምኑስ፡ዶለኝና፣
ዕድሜ፡እለምናለሁ፡ህይወት፡ጣፍጦኝና!
ህይወቱ፡ካልሞቀኝ፡ካልቆሰቆሰኩቱ፣
መቃብር፡እማይበጅ፡ከመኮራመቱ።
ቢከፋም፡ተረቱ።

ምን፡ጡር፡ይሆንብኛ፡
አለመጠየቄ፡የራሴን፡ኀሊናን፤
አለመማጠኔ፡የራሴን፡ልቡና!
ምንን፡ጡር፡እሠራ!

ምንን፡ጡር፡እሠራ —
ባማትሮ፡ብቻ፡አልፌው፡ብሄድ፡
በሰውነቴ፡ውስጥ፡የማየውን፡ጉድ!
ከሰውነቴም፡ውጭ —
ሲያፈጥብኝ፡ውሎ፡
እፍጦ፡’ሚያሳድር፣

በውን፡ የሚያቃዥኝ፡ የሚያባንነኝ፣
ብዙ፡ ታሪክ፡ አለ፡—
ሰሚ፡ ሰው፡ ቢገኝ።
ብዙ፡ ታሪክ፡ አለ፤ ብዙ — ብ — ዙ፡ ጉድ፤
ጉድ፡ አልዘረዝርም — ፍጅታው፡ የናንተ!
ማዳመጥ፡ አልበቃም፡ ላልተመለከተ፤
ተቅማጥ፡ በላው፡ ሲባል፡ ብዙ፡ ያመረተን፣ ብዙ፡ የከተተ!

ጥንታት፡ ሲያወሩ፡
ታሪክ፡ ሲቀፅሉ፣
አዝመራ፡ ሲሰምር፡
በሽታ፡ ነው፡ አሉ!

ሲባል፡ እንሰማለን።
እኛስ፡ ምን፡ አድምጠን፡ ምንድን፡ እናያለን?
ይህን፡ ታምር፡ ንግር፡
በማንስ፡ አንደበት፣ በየትኛው፡ ቋንቋችን፡
እንተረጉማለን?

፲፱፻፳፫ ዓ.ም.

## አስታራቂ፡ጠፍቶ

እምላክን፡ ሰድቤው፣
በጣም፡ ተበሳጭቶ፣
ከኔ፡ጋር፡ ማውራቱን፡ፈጠመና፡አብቅቶ፣
ቅር፡እንዳለው፡ሄዱ፤
ዞር፡ብሎም፡ አላየ ።
ሄዶ፡ ገሰገሰ፣
በስድቤ፡ተነክቶ፣ ልቡ፡እያለቀሰ።
ለናቱ፡ነገረ፣ እንድትገሥፀኝ—
　　ፍርድን፡ያውቃልና፤
ግና፡ ሁኖ፡ አልሆነም፣
ከእመቤቴም፡ ጋራ፡ተጣልተናልና።

፲፱፻፯፫ ዓ.ም.



# መዝሙር፡ዘሀበሻ

ምን፡አምኖ፡ይኑር፡ሰው፡ሁላ፣
ኧረ፡ምን፡አምኖ፤
የጥፋት፡አክሊል፡ከራሱ፡ጭኖ፤
ኧረ፡ምን፡አምኖ።
ምን፡በልቶ፡ይኑር፡ሰው፡ሁላ፣
ኧረ፡ምን፡በልቶ፤
እህል፡ሳይጠፋ፡አፉን፡ተዘግቶ፤
ኧረ፡ምን፡በልቶ።
ምን፡ይዞ፡ይጓዝ፡ትስብእት፣
ኧረ፡ምን፡ይዞ፤
ዘመን፡አመጣሽ፡እስክነነፍሱ፡ተግዞ፤
ኧረ፡ምን፡ይዞ።
ምን፡ብሎ፡ይሙት፡ሰው፡ሁላ፣
ኧረ፡ምን፡ብሎ፤
የሰው፡ባልሆነው፡ስድስ' ክንድ፡ዐፈር፡ተከልክሎ፤
ኧረ፡ምን፡ብሎ።
ምንን፡ንስሐ፡ይግባ፡ሀበሻ፤
ምኑንስ፡ይይዝ፡ሱባኤ፤
ሲወሰንበት፡ጦም፡ጦለቱ፡በባይተዋሮች፡ጉባኤ።

፲፱፻፳፫ ዓ.ም

ያንድ፡አፍታ፡ሽርሽር (ወይም፡የቂል፡ዘፈን)

ፈገግታዋ፡የደስታ፡አይደለም።
ኩርፊያዋም፡የቁጣ።
የንዴት — የመሰደብ፡እንጂ!
መከለሻው — ‘አንቺ፡ቆቱ!’— ሲጨመርበት፣
ቁጣዋ፡ይከሰታል፣ በደነዘዘ፡ፈገግታ፤
ጆሮዋን፡እንዲህ፡ላለ፡ቅሌት፡ዘግታ።

እንደኮምፒዩተር፣ እንደሞሉት።

እንደኮምፒዩተር፣ እንደሞሉት፣
እንዷ፡ታልፋለች፡ባጠገቤ፤
ከጎኗ፡ልጇን፡አሚቅላ፣
ካናቷ፡ቅርጫት፡ነገር፡ተክላ፣
በሁለት፡እጇ፡ቋጫ፡መሳይ፡እንጠልጥላ።

ፈገግታዋም፡የማሰነ።

ቅርጫቱ፡አይወድቅም — ያስደንቃል!
ጥበብ፡ነው — ኪነት፡ያለው!

ተብሎ፣
ሸራ፡ተወጥሮ፣ ቀለም፡ተቀላቅሎ፣
ምስኗ፡ይቀረፃል፡አምሮና፡አሽብርቆ።

የቆቱ፡ቆንጆ!

ይባላል።

አንቺ፡የቆቱ፡ቆንጆ!
ምስልሽ፡በሠላሳ፡ሣንቲም፡ተሸጦ፣
ቴምብር፡መሳይ፡ተለጥፎበት፡
ዓለሙን፡ይዞራል፤
ሥጋሽ፡ቢሉ፣ካለበት፡ተገትሯል።
ምስልሽ፡ነው፡የሚሄድ፣እስካሁንም፡የዘለቀ፤
ሥጋሽ—ሥጋሽ፡ካለበት፡ደርቆ፡ብዙም፡አልሄደ፤
ብዙም፡አልራቀ።

እንደኮምፒዩተር፣እንደሞሉት፡
እንደሞሉት፡
እንደሞሉት።

አዎ፣መቼስ፡ይሁና!
አግዜርሽ፡የሰጠሽ፡ውበት—ይህ፡የተፈጥሮ፡ቁንጅና፣
ስንቱን፡ሰዓሊ፡አስጠርቶ፣—በዝና!
ስንት፡ሺህ፡ብሮች፡አፍርቶ—በቂና!
ተሸጠ።
ዳግሞ፣እንደቆምሽበት፡መሬት፣በካሬ፡ሜትር፡አይለካም፤
በጋት—በሥንዝር፡ብቻ!
እንዳንቺም፡መሬት፡ጥዓቡን፡ጥሎ
በሩብ፡በሽልንግ፡የተገዛ፡ሳይሆን፣

ሊቃውንት፡የሚሻሙበት፣
የቁንጫ፡መላላጫ፡የሚወጣበት — ጥበብ፡ሆኗል፤
ለጉድ፡ለታምር፡ይታያል!

ግሩም፡እንጂ፣ግሩም፡አይደል!
እየህ፡ቅርጫቱን፡እንዴት፡እንደተሸከመች!
ደግሞ፡በጀርባዋ፡እንዲት፡ትንሽ፡ቆቁ፡
አዝላለች!
በሁለት፡እጇ፡ጮጮ፡መሳይ፡ይዛለች!
አይከብዳትም!አይደክማትም!
አቤት፡ይቺ፡ለማጥም!

ተብሎ፣
ከንፈር፡ይመጠጣል፡ዐይኖች፡እየሣቁ፣
ያንቺን፡ምስል፡ከበው፡ሊቆች፡ሲደነቁ።

መልሺላቸው፡እስቲ — አንቺ፡ምስል፣አንቺ፡ቆንጆ!
ሥጋ፡ለብሰሻል — የሚደክም፡የሚያመው!?
ትበያለሽ — ወይስ፣እህልም፡ትተሻል!?
ጉንሽ፡ደረቅ፡ነው — ተመችቶሻል!?
ቁጣሽ፡የምር፡ነው!? ፈገግታሽስ — የደስታ!?
ያን፡ሁሉ፡መንገድ፡ስትቆርጪ፣
'ትርኪምርኪውን'፡ስትሸጪ፤

እጅሽ፡ጭነት።

ራስሽ፡ጭነት ።

(እኛንትሽ፡ ብቻ፡ የለው፡ጭነት)

ሀብትሽን፡ባንዲት፡ስሙኒ፡ለማበርከት፣
እንዲያ፡ ስትሄጂ፡ አይደክምሽም !?
እውነት፡ታስገርሚያለሽ !?
ወይስ — እውነት፡ መልክሽ፡በቅቶሽ፣
ለሽራ፡ምስል፣
ላንዲት፡ የወረቀት፡ ቍንፅል፡በቅተሽ፣
ደስ፡ ብሎሽ፡ ትኖሪያለሽ !?
ለዚህ፡ ይሆን፡ ሁሌ፡ ፈገግታሽ፡ የማይጠፋ፡
እየማሰነ፡ ብቻ፡ የሚሄድ !?
እየማሰነ — እየማሰነ —— እ-የ-ማ-ሰነ !

አዎ! ቱሪስቶች፡ ይወዱሻል፤
የደስታ፡ ምንጭ፡ ነሽና !
እኔም፡ገጠምኩልሽ
(ወይስ፡ገጠምኩብሽ ?)
ቅኔ፡ ዘረፍኩልሽ
(ወይስ፡ዘረፍኩብሽ ?)
ወይስ —
ፈገግታሽ፡ኛላ፡ሁኖ፣ ግርጃ፡ሁኖ፣
ጎዶቶሽን፡ሸፍኖ፣
በትዝብት፡ ትጠይቂ፡ ይሆን
በዚያ፡በማናውቀው፡ ቋንቋሽ፤
በዚያ፡ በደነዘዘ፡ ፈገግታሽ ?

ትጠይቂ፡ ይሆን?
እንዲህ፡ ብለሽ — ንዴትሽን፡ ሸፍነሽ፤
'አይሰለቻችሁ፡ ይሆን፡ እናንተ፡
'በኔ፡ ዘላለም፡ መገረሙ
'እኔን፡ ዘላለም፡ ማድነቁ
'እኔን፡ ዘላለም፡ መመልከቱ?'

ይህ፡ ይሆን፡ ምሥጢሩ፡— የፈገግታሽ?
እየማሰነ፡ ቢሄድም፤
በደም፡ በሥጋ፡ የተዋሀደሽ?

ሀረማያ፤ ሰኔ፤ ፲፱፻፷፬ ዓ.ም.

## ታሪክ

እኛና፡እኔ፡ዱሮ፡ጥንት፣
ወትሮ፡ሲኖሩ፡ባንድ፡ቤት፣
ያስቀኑ፡ነበር፤ ለጋ፡ቢሆኑም፡ቀንበጥ፤
በለምለምነት፡ዘመናቸው።
ቁም፡ነገሩም፡ ይኼው፡ነበር — አብረው፡ባንድ፡ላይ፡መኖራቸው።

እኛ፡እኔነትን፡አቅፎ፡ዱባጮ፣
እኔ፡በኛ፡ውስጥ፡እፎይ፡ብሎ፡አርፎ፡
እንዳይኖር፣ የሚጠናወት፡ታሪክ፡መጣ፤
የእኛና፡የእኔ፡አንድነታቸው፡ላንዳፍታም፡ቢሆን፡ቅጡን፡ሊያጣ፡

እኔ፡እኛን፡ሰምቶ፡ሲኖሩ፣
እኛም፡እኔን፡ሹሞ፡ሲኖሩ፣ አንድነት፡ሰፍኖ፡በምድሩ፤
ኅሊና፡ድንገት፡አቀንቅኖ፡አእምሮ፡ድንገት፡ቢፈነድቅ፣
እኔ፡በዚህ፡ሁሉ፡መከሰት፣
ከኛ፡ፈጠረ፡ልዩነት።
እኛን፡ሊገዛው፡አሰበ፣ ዘዴ፡አቀላጥፎም፡ፈጠረ።
ዘዴው፡ተፈጥሮ፡እኔነት፣ እፎይ፡ገዛሁ፡ሲል፣በድንገት፣
እኛነት፡በርቆ፡በመንፈሱ፣
እኔን፡ቀስቅሶ፡ከትራሱ፣
ያባንን፡ጀመር፡ያቃዠው፤
በሱው፡በራሱ፡ዘዴ፡ገብቶ፣ እሱው፡ራሱ፡በቃኘው።

እናም፤
አመ፡ዛቲ፡ ዕለት፤
እኔነት፡ባኖ፡ድንገት፡ጠፋ፤
እኛነት፡ደግሞ — እንደኛነቱ፤ በእኔነት፡ዐፀድ፡ለምልሞ፤
እንደመቅድሙ፡ሊፋፋ፡፡

መጋቢት፤ ፲፱፻፷፫ ዓ.ም.



# አመፅ

የረሀብ፡እሥረኞች፡እጃችሁ፡ይፈታ፤
'እሱ፡ያቃል!' ብላችሁ፡ልባችሁ፡እያመነታ።
ማወቁን፡እንደሆን፡እግዜሩም፡ተቆታል፤
ሙታን፡አመፁና፡ከነሱ፡ይጧገታል።

ወሬ፡ከሻታችሁ፡እኔኮ፡አዳምጡኝ።
ከሙታኑ፡ዓለም፡እንደደረሰኝ፣
አምፀው፡የተነሱት፡የዋሀኑ፡ናቸው።
በምድር፡ባሉ፡ጊዜ፡የሰሙት፡ተስፋቸው፣
ከአርያም፡ሲወጡ፡ስላልሞላላቸው፣
በጥሞና፡እንዳይሆን፡በድናቸው፡ሰማና፣
ብድግ፡ብሎ፡አመጠ፡ነፍሱን፡ነጠቀና።

ግንቦት፣ ፲፱፻፷፫ ዓ.ም

## ያንድ፡አዝማሪ፡ዘፈን



አንቺን፡አይቼ፣
አንቺን፡በአእምሮየ፡ፀንሼ፣
እንደመንፈስ፡ሠርፀሽ፡በልቡናየ፡ስትከሰቺ፤
ልቤ፡ማኅደር፡ሁኖ፡ለኅብረ፡ቀለምሽ፡ሳስቶ፣
በስስ፡ልቤ፡ውስጥ፡ረቂቅ፡ፍቅር፡ተንሠራፍቶ፣
መንፈሴ፡በነፃነት፡ታብቶ፣ ግዘፌም፡መሬትን፡ሊለቅ፡ተነሥቶ፣
በ'ንዲህ፡ሁኔታ፡በጨረቃ፡ተመልክቶ፣
(በጨቅላነት፡ዘመኔ፡ስለማለት)
በልቡናየ — በልቤ — በሠራ፡አካላቴ፡
ልወድሽ፣ ነበር፡ቃል፡ገብቼ፤ አፍታ፡ሳልል፡ዱቂቃ።

ታዲያ — ድንገት፡ታዲያ፡ፀሀይ፡ሠርቃ፡
ዐይኔ፡ተከፍቶ፡የኅሊና፡የተኛ፡ልቤ፡ሲነቃ፤
ፀሀይ — ፀሀይ፡ቃጠሎ፡ያደበዘዘው፡መልክሽ፣
በጨረቃ፡በምሽት፡ትናንት፡ያየሁት፡ኅብርሽ፣
ቀለም፡ብቻ፡ሆነብኝ፡የተለያየ፤
ጨርቅ፡ብቻ፡ሆነሽብኝ፤
ንፋስ፡በጫፌ፡የሚመታሽ።
ዛሬን፡ሳይሽ፡በፀሀይ
(በውርዝውና፡ዘመኔ)
ሳይሽ፡ዛሬ፡በንፋስ፡ውስጥ፡ባየር፡ብቻ፡ስትረግቢ፣
ዛሬን፡ሳይሽ፡አተኩሬ፣ በፀሀዩ፣

ሳይሆን፡በዳመና፣
መንፈሴ፡ሸፈተ፡መና፡ሆንሽበትና።
ዛሬግ፡ሳይሽ፡አተኩሬ፣
በፀሀዩ፣በጠራራ፤
አንቺ፡ባንዲራ!
አንቺ፡ተውለብላቢ፡ጨርቅ!
አለ፣ አንድ፡አዝማሪ።

ግንቦት፣ ፲፱፻፷፫ ዓ.ም.



## ሀሩን፡ አልራሺድ

ከዕለታት፡ ባንደኛው፣ ሀሩን፡ አራሺድ፡
ከቤተ፡ መንግሥቱ፣
መጽሐፍ፡ ሲያገላብጥ፡ ልቡ፡ ተመሥጦ፣
ዙሪያው፡ ፀጥ፡ ብሎ፡ በሐሳብ፡ ተውጦ፣
ከገጣሞች፡ አንዱ፣ ከከያኒዎቹ፣ ከብዙቹ፡ መሀል፣
ያሠፈረውን፡ ቃል፣
እንዲህ፡ ሲል፡ ጀመረ።

ከወዴት፡ ደረሱ፤ ከምን፡ ጋር፡ ነፈሱ፤
እኒያ፡ ሁሉ፡ ነገሥታት፡ 'ርኩስ፡ ከቅዱሱ፤
እኒያ፡ ሥልጣናቱ፤
ዓለምን፡ ጨብጠው፡ ሕዝቡን፡ የገዙቱ፣
ባርያ፡ ያስነዱቱ፤
እኒያ፡ መኳንንቱ፣ አንድም፡ ወይዛዝርቱ።
ከወዴት፡ ደረሱ፤ ከምን፡ ጋር፡ ነፈሱ?

ኢለና፡— እንዲህ፡ ሲል፡ ቀፀለ።

ከነሞገሳቸው፣ ከነዘውዳቸው፣
ከነማ'ረጋቸው፣ ደግሞም፡ ከክብራቸው፣
ጎዳናን፡ ሊደዋል፡ የሩቅ፡ ሀገር፡ ሊደት፤
አንተም፡ ወዳጄ፡ ሆይ፡ ከማትቀርበት።
ዓለምን፡ ፈልገህ፡ ዓለምን፡ የመረጥክ፣
የምትሰጥህን፣
ብስል፡ ጥሬ፡ ሳትል፣ ሁሉንም፡ ያካበትክ፣

ዓለምን፡ ያፈቀርክ፣ ዓለም፡ የምትሻ፣
የምትሰጥህን፡ ውሰድ፤ አታመንታ!
ታዲያ፡ ግን፡ አስታውሳ!
ሞት ’ኮ፡ ዕዳ፡ አለብህ፡ የማታ፡ የማታ።
ይህን፡ ብቻ፡ እወቅ፡ ደግሞም፡ እንዳትረሣ!
ብሎ፡ ጠቀለለ።

ይህ፡ ሕግ፡ ተፈጥሮ — የምሩን፡ አምርሮ፣
ድንገት፡ ዱራሽ፡ መርዶ፡ ቢሆንበትና፣
ሀሩን፡ አልራሺድ፡ ካንገቱ፡ አቀርቅሮ፡ ከሆዱ፡ እንደባገ፣
ከመጽሐፉ፡ ገፅ፣ ከሚያነበው፡ ክፍል፡
ድንገት፡ ጠብ፡ አረገ፡ እንዲት፡ ዘለላ፡ እንባ።

ሄንሪ፡ ሎንግፌሎ፡ ‘ሀሩን፡ አልራሺድ’፡ በሚል
ርእስ፡ ከፃፈው፡ ተካቶ፡ የተተረጎመ።
ግንቦት፣ ፲፱፻፷፫ ዓ.ም.

## እየጠሩ፡ማባረር

አንድ፡ቀን፡ቅዳሜ፡ጠብሽ፡ወገረኛና፣
በእግሬ፡ልንሸራሸር፡ፒያሳ፡ወጣሁና፣
ዐይኔ፡ሲቀላውጥ፣ ልቤም፡ሲለው፡በርታ፣
ዐይኔ፡ቅልውጡን፡አቁሞ፡ላንዳፍታ፣
ሂዱ፡ትክል፡አለ — ካንዲቱ፡ኮረዳ፤
ሚጢጢ፡ነገር፤
ባላፍሮ፡ጠጉር።

ሚጢጢዋ፡ነገር፣ፍርጥምጥም፡ብላ፣
በቀኝ፡ዐይኗ፡ኮርነር፡እንዴ፡ገረፈችኝ፤
ስማይል፡አጠጣችኝ።
ስማይሏ፡ደግሞ፡ካተያይዋ፡ጋራ፡በሳል፡በመሆኑ፣
እንዲህ፡ያለ፡ብስለቱ፣ ሚጢጢ፡ገላዋን፡አለመመጠኑ፤
ይህ፡አንድ፡ላይ፡ሆኖ፡ደግሞም፡ምኑ፡ምኑ፣
ሚጢጢዋ፡ነገር፡እንዴ፡ስትዷቓ፣
ዐይኔ፡እንቅላፉና፡ልቤ፡ድንገት፡ነቃ።

ቆሜ፡እየኋት፤
ከመንገዱ፡ባሻገር፣ ካንዲት፡ትንሽ፡መደብር፡
ስትገባ።
ሚጢጢ፡ነገር፣ ገለባ፡የምታክል።
ጠበቅኋት፤ እስክትወጣ — ደሞ፡ላያት፣ ደሞ፡ልመኛት።

ብቻ — ሚጢጢዋ፡ ስትወጣ፣
ከጎኗ — አንድ፡ ት —— ልቅ፡ አፍሮ፣
ኃይለ — ኛ፡ የመሰለ፣ ግንባሩን፡ ኮስትሮ፣
ራ — መድ፣ ራ — መድ፡ ሲል፡ አይቼ፣
እኔ፡ ሆየ፣ እ — ጅጉን፡ ፈርቼ — ፈርቼ፣
ራሴንም — በጣ — ም፡ ታዝቤው፡ ታዝቤው፣ ታዝቤው፣
አፍሮንም፡ ስድቤው፣ ሰድቤው፣ ሰ — ድቤው፣

(በሆዬ)

ጠብሼን፡ አቅፌ፡ ተመለስኩት፣
ወደቅዳሜ፡ ሽርሽር፤
ወይ፡ የሚጢጢ፡ ነገር!
ወይ፡ ጠርቶ፡ ማግባረር!
እያልኩ።
በሆዬ።

ኅዳር፡ ፯፣ ፲፱፻፷፭ ዓ.ም.

## ኧረ፡ በፈጠረሽ!

ንግግር፡ አብቅቼ፡ አፌን፡ ተለጉሜ፤
ንግግር፡ አብቅተሽ፡ አልናገር፡ ብለሽ፤
ስለተኮራረፍን፤
ፀሀይ፡ ተሰበረች፣ አላበራም፡ ብላ፣
ጨረቃም፡ ጠፋችው፡ ደንግጣ፡ ኮብልላ፣
ዳግም፡ ጸቦ፡ ላትጥል፡ ተፈጥማ፡ ምላ!
እኔና፡ አንቺ፡ ብቻ፡ አለነው፡ ከዚሁ፣
ከኮርፊሽ፣ አኮርፌ፣
ኮርፍርፍ፡ ብለን፣
ፍጥረት፡ እስኪደንቀው፡ የእኛ፡ እንዲዚህ፡ መሆን።
ኧረ፡ በፈጠረሽ!
አንዴ፡ ሣቅ፡ በይና፡
ፀሐይ፡ ብልጭ፡ ትበል፣ ህይወት፡ ትሥረፅና።

፲፱፻፷፫ ዓ.ም.



# የዋህ፡ፍቅር

ሰማይና፡ምድር፡
ሁለቱ፡ተጋብተው፣
ሙሽራ፡ቤት፡ገብተው፤
ፀሀይ፡ኣቀንቅና፣
ተገልሞ፡ደመና፣
ሁሉም፡ሲደሰቱ፡
ተፈጥሮን፡ረስተው፣
በሀሴት፡ረክተው፤
ድንገት፡ሥቅቅ፡አሉ።
ሁሉም፡ተቃለሉ።
ፀሀይቱ፡አብቅታ፣አቁማ፡ቅንቀና፣
የመሬት፡የሰማይ፡— ሀሴታቸው፡በቃ፡ጋርዷቸው፡ደመና።
ታዲያ— ለዚህ፡ዓይነት፡ፍቅር፥
ሁሉም፡ሁኖ፡እንግዳ፣
ልዩ፡ናፍቆት፡ነግሦ፣
ምድር፡ሲቃ፡ቢ'ሃት፣
ሰማይ፡አለቀሰ፡እሷን፡ተንተርሶ።
ለዚህ፡የዋህ፡ፍቅር።

፲፱፻፷ ዓ.ም.



## ቡና?... ማኪያቶ?

ምክኑስ? አልኩ።

ነገሩ፡የምፀት፡ነው።

ብዙ፡አስቤ፡ተመራምሬ፣

በለቀምኩት፡የዕውቀት፡ፍሬ፣

በዚህ— የኔ-ዐዋቂነት፡ኢተኩሬ፣

ራሴን፡ከፍ፡አድርጌ፣ አክብሬ፣

በለቀምኩት—ባካበትኩት፡ፍሬ፡ዕውቀት፡ብዙ፡ኮርቼ፣

ከኩራቴም፡ብዛት፡

ብ—ዙ፣ እጅጉን፡ብ——ዙ፡ታብቼ፣ እ—ጅጉን፡ብዙ፡ቆይቼ፣

ድንገት — እንደው፡ድንገት፡

ጎዶሎ፡አንደበቴ፡ብትፈታ፣ አንዲት፡ጥያቄ፡ተጠይቄ፤

'ቡና፡ይምጣልህ፡ማኪያቶ?'

የምትል፤

'ለማንኛውም፣ እስቲ፡ጉዳዩ፡ይቅረብልኝ

'በመጀመሪያ፡ተጠንቶ'

ብየ፡ተናገርኩኝ፤

ጥናት፡ልምድ፡ሆኖብኝ።

ሊጠጣ፡የቀረበ፡ቡና፡—እናም፡ማኪያቶ፣

እንዲመለስ፡ሆነ፣ ሊቀርብ፡ተጠንቶ።

ሲጠና፣

ሁሉም፡በረደና፤
በርዱ፡ቆይቶ፡ቀረበና፤
በመብረዱ፡ተናቀና፤
ሊጠና፡የሄደው፡ማኪያቶ፣ ደግሞም፡ቡና፣
ተጎልቶ፡በዚያው፡ቀረ፤እንዳልነበረ፡ተረሣና።
ደግሞ፡እስኪፈላ፡ሌላ፡ቡና።

መጋቢት፣ ፲፱፻፺፯ ዓ.ም.



# ዕፀ፡በለስ

በለሴ፡ሁነሽ፣
ልምላሜሽ፡ የስሜት፡ ልቤን፡የሚመታ፣
እንዴ፡ብቻ፡ገምጬሽ፡በፍርሃት፡ሳላመነታ፣
እርቃንነቴን፡ባወቅሁት።
ደመ፡ነፍስ፡ህይወት፡ባላልጋየኝ፡ባስነሣሁት፣ባነቃሁት።
ከዚያም፡ብሰዴድ፡ባልከፋኝ፡—
አለሁበት፡ለሚባል፡ገነት፡ባይተዋር፡ሆኜ፤
ሰውነቴን፡አውቄ፣አዳምነቴን፡አስተንትኜ።
ዕፁብ፡ሚጠትን፡እንዳደርግ፡ወዳንቺ፡
ዕፁብ፡ተራክቦን፡ካንቺ፡ጋራ፣
ለስሜቴ፡በለስ፡ሁኚኝ፤ አትጠውልጊ፡አደራ።
በለሴ— በለሴ!
እንዳልሆን፡የስሜት፡ብቻ፡ቊራኛ፣
እንዳልሆን፡የስሜት፡ብቻ፡ብቸኛ፣
አሁንም፡ደግመሽ፡ለምልሚ፡እልፍ፡ሺ፡ዘመን፡እንዳልተኛ።
ራቌን፡መሆኔን፡አብስሪኝ፡ብትመሪም፡ቅሉ፡ባውቀው፣
ስሜቴ፡ብቻ፡ተንሠራፍቶ፡የሰው፡አ'ምሮየን፡እንዳይጨንቀው

መጋቢት፣ ፲፱፻፷፯ ዓ.ም.



# ምኞት፡ፈረስ፡ቢሆን...

...ዓለሙን፡ጠፍጥፌው፡ቂጣ፡በጋገርሁት፣
ውሀውንም፡ነጩ፡ቅቤ፡ባወጣሁት።
ባወጣሁት፡ቅቤ፡ቂጣየን፡አርሼ፣
ጩጩብሳ፡ጭብጦ፡አድርጌ፡ለውሼ፣
አንዴ፡በገመጥሁት — አንጀቴን፡ባራስሁት።
የዋጥሁትን፡ውጩ፡ የሰለቀጥኩትን፣
ከዚያ፡'ሚተርፈኝን፡—
ምኞት፡ኃይል፡ቢሆን —
ያድበለበልኩትን፡ጩጩብሳ፡ጭብጦ፣
ትንፋሽ፡ለቅቈበት፣ ከእጄ፡ነፃ፡አድርጌ፣
አጉልቼ —— አሳድጌ፣
ዓለሙን፡በተውኩት፡በመሬትነቱ፣
ዳግመኛ፡እስክመኘው፣ ሊሆን፡እንዴጥንቱ።
ብቻ — ምኞት፡ፈረስ፡ሁኖ፡አይጋልብም፡ሜዳ፡የሽምጥ፡አይሄድም
ደንገላሣ፡አይመታም፤ ሶምሶማም፡አይረግጥም።
እና፡የኔም፡ውሀ፡ቅቤ፡ሁኖ፡ቀልጦ፡ጭብጦ፡አያሠራም፤
የሚሾረው፡ዓለም፡ምኞቴን፡አይፈራም።
ገላምጦኝን፡ያልፋል፣ ሳይፈታ፡ሬቱ፣
በሕግ፡ተፈጥሮው፡በታሪክ፡ሥራቱ፣
ዓለም፡እንደወትሮው፡ዓለም፡እንዳጥንቱ።

መጋቢት፣ ፲፱፻፷፮ ዓ.ም.

# ምፀት

ሁላችንም፡ነን፡
ወንድማማቾቹ፤
እንደቃየል፣ እንደአቤል፤
እንደሁለቱ፡ የአዳም፡ ልጆች ።

ከጆን፡ፖከር፡ግጥም፡የተተረጎመ
፲፱፻፷፫ ዓ.ም.

# አታድርስ!

መዝጊያዋን፡ቆርቍሮ
ድምፏን፡ባታሰማ፣
ሽቶና፡ጠይቆ፡ቀጓጆ፡ብታቅማማ፣
በሌሊቱ፡ግርማ።
በጠራራ፡ፀሀይ፡ካደባባይ፡ወጥቶ፣
ድምፁን፡ከድምፅ፡ይልቅ፡ሺህ፡ጊዜ፡አጣፍቶ፤
'ቆዳየም፡ ይገፈፍ፡ ይሁንልሽ፡ጫማ፡
'እኔ፡ምን፡ቸገረኝ፡ላንቺ፡ከተስማማ'
ብሎ፡አንቆረቆረ፡
የጊዜውን፡ዘፈን፣ የዘመኑን፡ዜማ።

## ጊዜን፡ተፍቼበት

ጊዜን፡ንቄው፣ በጎን፡ተመልክቼ፣
ምላሴን፡አውጥቼ፣ ምራቄን፡ተፍቼ፣
እንዳይሸጥ፡እንዳይለወጥ፡አድርጌ፣
ስድብ፡አውርጄበት፣ ዛቻን፡ጨምሬበት፤
ይህን፡ ሁሉ፡አድርጌው፤
"ስድብ፡አይለጠፍ!
"ታዲያ፡ምን፡አለበት!"
ብሎ፡ካለኝ፡ኋላ፤
ቀና፡ብሎ፡ላያይ፡ቃል፡ገባልኝና፡
አይሥቁ፡ሣቅ፡ሥቆ፣ ዝም፡ብሎኝ፡አለፈ፣
ከቶ፡ምን፡ቸግሮት፤ ምን፡ዱንታ፡አለውና!
ከቆምኩበት፡ትቶኝ።

በቀደምለት፣ ፲፱፻፷፫ ዓ.ም.

## ራእየ፡ግምበኛ፡ዘአራዳ፡ጊዮርጊስ

ህይወት፡የወጠነለት፣ወይስ፡የወሰነበት፤
የዐርባ፡ቀን፡ዕድሉ፡የጫነበት፡አክሊል፡ይሆን?
በተለይ፡ግዘፉ፡ረቂቅ፣መንፈሱ፡ግዘፍን፡ነሥቶ
ግዘፍን፡ነሞቶ፡ይሆን
የህልውናው፡ዘይቤ፡ይከሰትለት፡ዘንድ፡ያበቃው?

ወይስ

'ኅሩያን፡በህልውናሆሙ፡ጻድቃን፡

በሕገጋቲሆሙ

'ልዕሉል፡ከመ፡መዓልው፡በፋትሆሙ'

ተሰኝተው፣—በመላእክት፡ቋንቋ፤
ከእንጨት፡መርጦ፡ለታቦት፤ከሰው፡መርጦ፡ለሹመት፡
እንዲሉ

'ዘኀረዩ፡አርእስቲሆሙ'

እኒህ፡የመፀወቱት፡ትሩፋት፡ጊድራት፡ይሆን፡
ለማኅበረ፡ሰብ፡ባይተዋር፡መሆኑን፡ሹክ፡የሚልለት?
እውነታውስ— እሱም፡

ለባዊ፡መሆኑ፣
ነባቢ፡መሆኑ፣
ገባሪ፡መሆኑ።

ብቻ፡የማይገባው፡
ሐገ፡ኅሩያን፡የሱን፡ሰውነት፡ሲለካ፡
ሰብእናው፡የተገላቢጦሽ፡በኅዳጣኑ፡ጠገግ፡ሲጠለል፡—

ዖኜ፡ነው፡የማይገባው።
ቋንቋው፡የመላእክት፡ሁኖበት።
ምሥጢሩ፣
ጥበበ፡ነገሩ፣
'የመለኮት፡ባህርይ'፡ምሥጢሩ።
ባንድ፡ጠገግ፡ጭንቅት፡—
ስለት፡ሲያብጥ፣
ጥማት፡ሲያንቅ፣
ግራ፡እየገባው።
ባንድ፡ጠገግ፡ጥበት፡—
ሰው፡ማስቸገሩ፡
ሲያጣ፡ማፌሩ።
ሁለቱም፡አንድ፡ናቸው፡ለነገሩ።
ብቻ፡ሁሉም፣ ሰብእናውን፡እየወጋው፡—
ትዓሸም፡ቢሉ፡ጠቅታ — መከፋቱ።
ባንድ፡በኩል፡ተስፋ፤ ደግሞ፡ነገ፡ምኞቱ።
መከፋቱ — ተስፋው — ምኞቱ (ተው፡ቻለው፡ሆዴ፡ያለኝን?)
ማጣቱ፣
ምሬቱ፣
ቁጣው — ንዴቱ —
እብደቱ — እብደቱ — እብደቱ!
እንጃ! ሌላው፡ዘፋኝ፡ልክ፡ብሏል፤
ከልክ፡በላይ፡ የታመቀው፡ይፈነዳል።
ወይ፡ይገድላል
ወይም፡ደግሞ — አይግረመንና — ይሞታል።

ጥር፣ ፲፱፻፷፪ ዓ.ም

# ጨረቃ

፩

ጨረቃ፣ ድንቡል፡ቦቃ፣
ጊዜ፡ባለዕጣ፡አድርጓት፡በፈረቃ፣
ከአጼ፡ቤት፡ቁልፊት፡ተላቃ፣
ድቅድቅ፡ጨለማን፡ገፋ፣ ጠረር፡ሸንተረሩን፡አጥለቅልቃ፣
ትመራው፡ያዘች፡ተጋዳዩን፡
ታሳየው፡ወጣች፡የሰበረ፡ሰካ፡ጎዳናውን።
ጨረቃ፡ድንቡል፡ቦቃ፣
ከአጼ፡ቤት፡ነጥቃ፡ለቃ፣
ከተጋዳዩ፡ሰፊ፡ሜዳ፣ ከጠረር፡በላይ፡ደምቃ፡—
ከጠረር፡ያሉ፡ተጋዳዮች፡
ተኮሱ፡ተኳኩሱ፤
ጠላትን፡ደመሰሱ፤
ደረቅ፡ቋጣ፡ሪፋ፡ቆሎ፣
አጼን፡ትተሽ፡ከኛ፡ቶሎ፤ — ብለው፡ያወደሷት፣
በፀሀይ፡ቦታ፡ቅርሴ፡ብለው፣ በሌት፡ባድማ፡የጠቀሷት፤
ፍቅረኞች፡የብቻ፡ብለው፣ ማር፡ጥፍጥናዋን፡ሲቀምሱ፣
ታጋይም፡ደግሞ፡የብጤቱን፣ ትጥቁን፡አድርጎ፡ትራሱ፣
ያወድሳታል፡በግብሯ፡
ያዜምላታል፡በውጤቱ፣
ጨረቃ፡ውቢቱ፣ ፀሀይ፡የሌሊቱ።
ህልውናዋ፡የነበረ፡በግቢ፡ቁልፊት፡ተወስኖ፣

አዳር፡ጉዞዋ፡የዘመኑ፡ከተጋዳዩ፡ጣምራ፡ሆኖ፣
ተመራው፡ያዘች፣
ፋና፡ሁና፡በሌት፡— አቅፏ፡ደግፏ— ዱካውን፡እያሳየች።

፱

ጨረቃ፡ድንግል፡ቦቃ፡
ሀፍረት፡ሁሞባት፡መጋለጡ፡በደመና፡ጀርባ፡ተደብቃ፣
ደብዘዝ፡ባለ፡ፈገግታ፣ በለሆሳስ፡ፍቅር፣
የታጋይ፡አርምጃውን፡ስትማትር፣
ስትስብ —— ስ-ታስ-ጠ—ጋው፣
ድንገት፡ጩኸት፡በረከተ፤
ታጋይ፡ተኩሱን፡ከፈተ፣
የጠላትን፡ኬላ፡አነካከተ፤
ጨረቃ፡ፍቅሩን፡ተመለከተ።
ጨረቃም፡ድንግል፡ቦቃ፣
ሀፍረት፡ሁሞባት፡መጋለጡ፡ሬት፡የነበረች፡ተደብቃ፣
ዕርቃን፡ብርሃኗን፡ወረወረች፤
ከደመና፡ግርዶሽ፡ወጥታ፡ተፍለቀለቀች፣
ዐይኗ፡ጥላዋ፡ተገፎ፡ዕርቃኗ፡ምድሩን፡አለበሰች።
ሜዳ፡ሸንተረር፡ተኳኩሎ፡ከጨረቃ፡ጋር፡ተጣቀሰ፤
ታጋይ፡ውበቷን፡አወደሰ — መጋለጧንም፡ቀደሰ።
በዚች፡ዕርቃን፡ብርሃን፣ ከዚች፡ዕርቃን፡ብርሃን፣
ከታጋይ፡ተራክቦ፡
ድል፡ተወለደና፡የሰው፡ልጅ፡ታወቀ።
ታጋይ፡ፈነደቀ! ታጋይ፡ፈነደቀ!

፲፱፻፷፩/፷፪ ዓ.ም.

## አዲስ፡ ግጥም

እግዜር፡ ትእዛዙ፡ ተሸሮ፣ ቃል፡ ቃልነቱ፡ ባይከበር፣
አንዲት፡ ፍሬ፡ ተበጥሳ፣
አንዲት፡ ፍሬ፡ ተቀምሳ፤– የገነት፡ መውጫው፡ ቢሰበር፣
በዚህ፡ ተቆጥቶ፣
 ‘አዳም፡ አባተ፡ ሔዋንም፡ ደግሞ!’
ብሎ፡ ተጣርቶ፣
 ‘ያላቆጠ፡ ያደበለበላችሁ፡
 ‘እጄ፡ ሳያጠፋችሁ፣
 ‘ውጡልኝ፡ ከዚህ! ውጡልኝ፡ ብቻ!
 ‘ከዚህ፡ ያቆማል፡ የትዕግሥቴ፡ ዳርቻ!’
አለና፣
አዳምን፡ (ከነሚስቱ) ‘ብላዕ፡ በህፈ፡ ገጽከ!’
ብሎ፡ ሲረግመው፣
አዳምነቱን፡ ቀደሰ፤
በዚህም፡ የገነት፡ ኪዳን፡ ፈረሰ፡
የገነት፡ ድንበር፡ ተጣሰ።
ቁልቁል፡ ውረድ፡ ሲለው፡ ወደምድሩ፣
አዳም፡ ከነሚስቱ፡ በእዱ፡ ጥበብ፡ ሙያ፡ ክበሩ።
ተልዐሉ፤ ዐረጉ፤
ተቀራኛቸው፡ ቅዱስ፡ ሰይጣን፡ ሠርቶ፡ የመፍጠር፡ ማዕርጉ!

አዳም፡ከፈጣሪው፡ቢጣላ፣
የፈጣሪነት፡ክሂሎቱ፡በተረገመው፡ቤቱ፡ሲሞላ፣
ቃል፡ግዘፍን፡ነሣ፤
ነፍስ፡አካልን፡ገዛ፤
አዳም፡ትስብእት፡ቆመ፡በእዱ፡ጥበቡ፡ቤዛ።
ዳንጊያን፡ከዳንጊያ፡አማርጦ፣ ዳንጊያን፡ከዳንጊያ፡አፋጭቶ፣
ብዙ፡ፈጠረ፤ ብዙ፡አመረተ፤
በመፍጠሩ፡የሰውነቱ፡ውበቱ፡ተከሰተ።
በወዝህ፡ብላ፡ተብሎ፡መረገሙ፡ቡራኬ፡ሆኖ፡ተገኘ፤
የሰውነቱን፡ልዕልና፡በተፈጥሮ፡ውስጥ፡እየናኘ።
ዳንጊያን፡ከዳንጊያ፡አዋቅሮ፣ ዳንጊያን፡ከዳንጊያ፡አማርጦ፣
በእዱ፡ጥበቡ፡አስጊጦ፤
ቃልን፡በዳንጊያ፡ግዘፍ፡ኃይል፡ግዘፍ፡አሲዞ፡አግዞ፣
ከምድር፡ቢያወርደው፡ጊዜና፣
ቃሉ፡ፍፃሜን፡አገኘ፡አዳም፡የሰው፡ልጅ፡ሆነና።
ቃል፡ቍልቍል፡ወረደ፤
ፍፁምነቱ፡በዳንጊያ፡ግዘፍ፡ታገደ፤
በወላድ፡ምድር፡ማኅፀን፡የኪነት፡እሳት፡ነደደ።
አዳም፡ወለደ፣ በሥቃይ፡በሲቃ፣
ቃልን፡ጨበጠና፣ ሥጋ፡አለበሰና፤
ተፈጥሮን፡አድንቆ፣ ተፈጥሮን፡መልምሎ፣ ተፈጥሮን፡አርቆ፣
በእዱ፡ጥበብ፡ሙያው፡ራሱን፡መርቆ፣
ደግሞ፡በፈረቃ፡
አዳም፡ቀንጆን፡ወልዶ፡ለአብነቱ፡በቃ።

፲፱፻፸፩ ዓ.ም.

## የመኖር፡ምፀቱ

አሁን፡-እዚህ።
አሁን— በዚች፡ደቂቃ፤
በምጥ፡የተያዘች፡እናት፡በታላቅ፡ሕማም፡ተጨንቃ።
ጭንቅም፡ቢሉ፡ግና፡በዚች፡ደቂቃ፡
ይችው፡ወላድ፡በህይወት፡ጀርባ፡ተደብቃ፣
ስታቃሥት፡-በሥቃይ-በሲቃ
አንዲቷ፡ደቂቃ፡አለፈች።
ጊዜም፡በዚያው፡ልክ፡ተራምዶ፡ደግሞ፡በዚያው፡ልክ፡አጠረ፤
አንድ፡የሕይወት፡አምሳል፡ዐይኑን፡ወደዚች፡ዓለም፡ማተረ፤
ህፃን፡ተወለደ።
ግና፡ደግሞ፣ በዚያች፡አፍታ፡የአንዲት፡እናት፡ህይወት፡ታገደ።
ባንዲት፡አፍታ!
አንዲት፡ደቂቃ፡ስታልፍ፡ሌላ፡ደቂቃ፡ተተክታ!
በዚህ፡ፅፁብ፡ሂደት፡—በዚህ፡የእድገት፡ምሥጢር፣
ከዕቃ፡ወደዕቃ፡እንደሚገላበጥ፡ነገር
ስትፈሥ፡ስትሞላ፡የሰው፡ህይወት፣
በዚህ፡ፅፁብ፡ትንግርት፡በዚህ፡ዕፁብ፡ሥራ፡
ህይወት፡አንድ፡አምባ፡ለቃ፡ሌላ፡ማኅደር፡ስትሠራ፣
ዕፁብ፡እንጂ፣የሚያስደምም፡ዕፁብ፡ሥራ።
እነሆም፡ደግሞ፡በዚህ፡አፍታ፡
በዋይታና፡በዕልልታ፣
ልብ፡ተሰንጥቆ፡ሲያመነታ፣

ከዚህ፡ግዑዝ፡ብዕር፣ካንዲት፡የቀለም፡ጠብታ፣
የመኖርና፡ያለመኖር፡መራር፡ቅኔ፡ከነምፀቱ፡ተፈታ።
አንድ፡ህፃን፡ሲወለድ፡— አንዲት፡እናት፡ሙታ።

፲፱፻፷፪ ዓ.ም.

## ክብሪት

አንድ፡ ተሽ—ሽታ — ጣ-ጣ-ጣ-ታ፣
የሥቃይ፡ድምፅ፡— የቃጠሎ፣
አንድ፡ሹክታ — በለሆሳስ— እፎ—ይታ፣
ከዚያ፡ዱጣሞ፡ከባድ፡ዝምታ።
አንዲት፡ክብሪት፡ስትሞት፣ነዷ፡ተቃጥላ፣
ዕጣዋ፡እንጂ፡ነው፡ተባለና፡
እንደማንኛውም፡ነዳጅ፡እንደሌላ፡ክብሪት፡ሁላ።
ሥቃይ

ሲቃ

እፎይታ

ዝምታ

ክብሪት፡ነዷ፣ ክብሪት፡ሞታ።

፲፱፻፷፬ ዓ.ም.

# የስሜት፡ንፃሬዎች

## ፩

ዛሬን፡በመንገድ፡ላይ፡ስዳክር፡ቆይቼ፣
አላፊ፡አግዳሚውን፡
አፍሽ፡አጎንባሹን፡
በፈርጁ፡ለይቼ፤
ሳበጥረው፡ውየ፡መሸ፡ሳበጥረው፣
ስንዴና፡እንክርዳዱን፡ጨርሼ፡ሳልለየው።
ሁሉም፡ተዛነቀ፤
በመለየት፡ሲቃ፡በእንባ፡ተናነቀ።
ራሱን፡አቀፈ፣ሳመው፡አገላብጦ፤
አይዞህ፡ባዩን፡ቢያጣ፡ጊዜው፡ተለውጦ።
(እጉል፡ጊዜ፡ብሎ)
እጉል፡ጊዜ፡አንበል፡ጊዜ፡ምን፡አጠፋ፡
ቢያቀኑት፡ሊቀና፡ቢደፉት፡ሊደፋ።
አቅኚ፡አዘናባዩ፣
ህይወት፡ሰጭ፡ገዳዩ፣
የኛው፡እንቅስቃሴ፡ብቻ፡እንጂ፡ነውና፣
ብዙ፡ምች፡አይምታን፤ እንየው፡በጥሞና፤
አንጋለጥ፡ብዙ።

ስሜት፡ራዱ፤
ወኔ፡በረዱ፤
ኅሊና፡አደገደገ

ሂዷት፡ማለገ።
እንበስል፡ሲሉ፡ፀሀይ፡ገሮ፣
የተጣደው፡አሮ፣
አብሽሎ፡እንኳ፡አልሆነም፡መረረ፤
ወገን፡ከወገኑም፡አልተቋጠረ፤
ወኔ፡ታነቀ፤
አእምሮ፡ከስሜት፡በእንባ፡ተዛነቀ፤
አለቀ፡አሉና፡ደቀቀ።
አሁን፡ተምን፡ጊዜው፡ማተቡ፡ወለቀ።

፪

እሳትስ፡ነድዶ፡ነበር።
የተስፋ፡ምላሱ፡የነፍስን፡ጠሊቅ፡ማኅደር፡እያሞቀ፣
በፍሥሐ፡ወሀሴት፡ፅርሐ፡አርያሙን፡ሊዳስ፡እየነጠቀ፣
ህያውነቱን፡ሊያፀድቅ፣
እመቀ፡እመቃቱን፡ሊለቅ።
ሊበር፣ሊወረወር፣
ከኮከብ፡ጋር፡ሊሰምር፤
ዓለመ፡ዓለማቱን፡ሊሞላ፣
በረድን፡አቅልጦ፡ሊጄላ፣
ህልም፡መሆኑን፡ሳያውቅ።
የሰው፡ልቤ፡እንዲህ፡እያለ፡ሲያሰላ፣
እሳት፡ቀብጦ፡
በረድን፡አቅልጦ፣
ባንዲት፡የውሃ፡ጠብታ፣

ከለሁ፡ ይል፡ የነበር፡ የነፍስ፡ እቶን፡ እሳት፡
በበረድ፡ ተፈታ።
እናም፡ በፈረቃ፣
እናም፡ በፈረቃ፤
እሳት፡ በረድ፡ ሆኖ፡ በረድ፡ አቃጠለ፤
ባያል፡ ቅዝቃዜ፡ ነፍስ፡ ተቃጠለ፤
ኩምትር፡ ኩምትር፡ አለ።
እሳት፡ ተሸነፈ፤
በሞቀው፡ ነፍሴ፡ ውስጥ፡
አንድ፡ ትልቅ፡ በረድ፡ ገብቶ፡ ተወተፈ።
እውነቱን፡ ለፈፈ።
ነፍስ፡ መታመሙን፡ በቆፈን፡ ተይዞ፡
በምናብ፡ እውነታ፡ ታሥሮና፡ ተግዞ።

፫

በመጀመሪያ፡ ፍቅር፡ ነበረ።
ፍቅርም፡ የሰው፡ ሆነ።
ፍቅር፡ አካል፡ ሲገዛ፣
ነፍስ፡ አግብቶ፡ ሲተነፍስ፣
ሙቀቱ፡ ህይወትን፡ ዘራ፤
የስሜትን፡ ፋና፡ አበራ።
በዚህ፡ ጮራ፡
በሰውነት፡ አምባ፣ በሰውነት፡ ጎራ፡
ወበራ፡ ተደግሶ፣
ካዓድ፡ ማድጋ፡ ፋት፡ ተብሎ፣ ካንድ፡ መሥሪያ፡ ተቆርሶ፣

ባንድ፡በልቶ፡ጠጥቶ፣
ባንድ፡አውርቶ፤
ደስታን፣ተስፋን፣
ድካም፡ብርታቱን፡ተጫውቶ፣
ተስማምቶ፡ተግባብቶ፣
ልብ፡ለልብ፡ተጎራብቶ፣
ባንድ፡ምግኜ፣ባንድ፡ዜማ፣
ሁለት፡የተለያየ፡ነፍስ፡ቃል፡አልባ፡ሲስማማ፣
አንዱ፡በሌላው፡ሁኖ፤
አንድነት፡ፀፀድቃል፤ፍቅር፡ደግሞ፡ይሠርቃል፤
ነፍስ፡ዘርቶ፡ያፈካል።
ትስብእት፡ሊሰግድለት፣
ሐውልት፡ሊቀርፅለት፣
በአምሳሉ።

፲

መናኸሪያውን፡ሥቶ፡ዛሬ፡የባከነ፡ስሜቴ፣
ጭጋግ፡ደመና፡ሽፍኖት፡ማለም፡ያቃተው፡አስተያየቴ፡
አልጠራ—አልሰማ፤
አላረካ፤አላመረቃ።
በዱሙ፡ነፍስ፡ጉዞ፡ባገኘበት፡ቃርሞ፡ሊያበቃ፤
ቢጠግብ፡ሊጋደም፡ቢራብ፡ሊያዛጋ።
ጥርስ፡አልነጭ፡ብሎ፡ማኘክ፡ተስኖት፡መንጋጋ፤
ቀን፡በመሽ፡ሌት፡በነጋ፡
አንድ፡ምዕራፍ፡በዘፈቀደ፡ተከፍቶ፡በዘፈቀደ፡ሲዘጋ።

ውሉ፡የጠፋበት — መልህቁን፡ያልጣለ፡መርከበኛ፣
አይንቀሳቀስ፡ዝግ፡ሁኖበት፣
ማዕበል፡አይሎበት፡አይተኛ፤
ግራ፡የመጋባት፡መጋኛ፡እያጮለው።
አላልቅ፡የሚል፡ተስፋ፡ደግሞ፡እያማለለው።
ተጠምዶ፡ተጋርዶ፤
ታሥሮ፡ተቆንድዶ፤
ጋይቶም፡ይሁን፡ነዶ፤
ጠልቶም፡ይሁን፡ወዶ፣
ዛሬን፡ለነገ፡ያማጣል፤
ዐመድ፡ሊለብስ፡ይወዛል።
ምን፡ስም፡ይውጣ — የክርስትናም፡ይሁን፡የዳቦ፡
መለዮ፡ጠፍቶለት፡እንኪያስ፡ኪቀር፡አልቦ።
እስቲ፡ስም፡እውጡለት፡ለዚህ፡ለክስተቱ፤
ኢልሆንልኝ፡ቢለኝ፡እኔ፡ባለቤቱ።



## ትንሽ፡ኮከብ

ስትርቅ፡እየጎላች፣ስትቀርብ፡እያነሰች፣
ለትርጉም፡ላንድምታ፡ፈጽሞ፡ያስቸገረች፣
አንዲት፡ትንሽ፡ኮከብ፡ውብ፡ብርሃን፡ነበረች።

ከሩቅ፡ስትጠቅሰኝ፡
እተኩሬ፡ሳያት—
ሳያት፡ስማትራት፤
እልፍ፡አእላፍ፡ጨረሮቿ፣የብርሃን፡ጣቶቿ፡ሲዳስሱኝ፣
የሠራ፡አካላቴን፡ሲዳብሱኝ—በዝምታ።
በልቅረብ፡አልቅረብ፡መንታ፡መንገድ፡ተሰንጥቄ፡ሳመነታ፣
ጠበቅ፡አድርገው፡እንዲይዙኝ፡ስመኛቸው፣
ወትሮ፡ሲያማልለኝ፡የሩቅ፡ዝምታ፡ሙቀታቸው፣
እልፍ፡አእላፍ፡ጨረሮቿ፣
እኒያ፡የረቂቅ፡ብርሃን፡ጣቶቿ፣
ያንዲት፡ትንሽ፡ኮከብ።
ይህችን፡ሩቅ፡ፈለግ፡ብርሃን፡ቀርቦ፡የማየት፡ፍላጎቴ፣
ፈተናየ፡እጅግ፡በዝቶ፣
በምሕዋሯ፡ተጠምዶ፣ግን፡በርቀቷ፡ታግዶ፤
አንድም፣
ለብ፡ባለ፡ሙቀቷ፡ሊታጠብ፡ሲሻ፡ህይወቴ፣
የማላውቀውን፡ቃጠሎዋን፡ደግሞ፡ወትሮ፡ሲፈራ፡ሰውነቴ—
ሥጋ፡ሥሡነቴ፤

አንዲት፡ትንሽ፡ኮከብ።
ምኞቴ — ለብ፡ባለ፡ሙቀቷ፡ህይወቴ፡ሊታጠብ፡ሲሻ፣
ፍርሃቴ — ከእልፍ፡አእላፍ፡የ'ሳት፡ላንቃዋ፡ሥጋየ፡ቢያጣ፡መሸሻ፤
ባሕርይዋ፡ኅቡእ፡ሁኖ፡ዕውቀቴ፡ጠፍቶት፡መዳረሻ፤
የሩቅ፡ማኅቶት፡ብሕትውናዋን፡መረዳቱ፣
አልወጣ፡ብሎኝ፡መርምሮ፡የማወቅ፡አቀበቱ፣
ወድቆ፡የመነሣት፡ብላቱ፣
ተቃጥሎ፡የመብረድ፡እርካቱ፣

ያንዲት፡ትንሽ፡ኮከብ።
በዝምታ፡ትግል፡ውስጥ፡ፈንጠር፡ብላ፡መጥቃ፣
የምታበራ፣ ህዋውን፡ሰንጥቃ፣
የብርሃን፡ኢጣቢዋን፡ካድማስ፡ባሻገር፡ፈንጥቃ፡
ዓለሙ፡ዓለማቱን፡ትገን፡አርጋ፣ ሰፊውን፡ፅልመት፡ንቃ፤
ስትርቅ፡እየጎላች፣ ስትቀርብ፡እያነሰች፣
ለትርጉም፡ላንድምታ፡ፈጽሞ፡ያስቸገረች፣
አንዲት፡ትንሽ፡ኮከብ፡
ውብ፡ብርሃን፡ነበረች።

ብርሃን፡ሁና፡ጠልቃ፡በልቤ፡ልምሹ፣
አልሠርቅ፡እያለችኝ፡ቀናቱ፡ሲመሹ፣
የምታቀዝዘኝ፣
አንዲት፡ትንሽ፡ኮከብ፡
ውብ፡ብርሃን፡ነበረች፤
ስትርቅ፡የምትጎላ፡
ስትቀርብ፡እያነሰች።
አንዲት፡ትንሽ፡ኮከብ።

አንዴ፡ደብዘዝ፣ አሁን፡ቀዝቀዝ፣
አንዴ፡ደመቅ፣ ደማሞ፡ፈካ፣
ቢርቋት፡ አትጠፋ፣ ቢቀርቧት፡ደማሞ፡'ማትነኻ።
አንዲት፡ብቸኛ፡ኮከብ፣
አንድ፡ብቸኛ፡ልብ፣ ተውጠው፡በዝምታ፣
ቄሱም፡ዝም፡ መጣፉም፡ደማሞ፣
እንዴት፡በዝምታ፡ ሰው፡ይሞታል፡ታሞ።
ባንዲት፡ትንሽ፡ኮከብ።

ያቺ፡ትንሽ፡ኮከብ፣
ተወርዋሪ፡አይደለች፤
አላየው፡ፈለጓን፣ የብርሃን፡ትንግርቷን።
የኅሊና፡ክበብ፣ የአእምሮ፡ጥበቱ፡
ባዕድ፡ለክስተቱ
ታቃጥለኛ፡ታሙቀኛ፡እንደምን፡ልረዳ፣
ወትሮ፡እየተያየን፡ዘላለም፡እንግዳ።
መናገር፡ተሥኖት፣ መሞከር፡ተሥኖት፡
የሰው፡ ሰውነቴ፡
ባጉል፡ልማድ፡ፍርሃት፡ሲገደብ፡ስሜቴ፣
ኮከቢቱ፡ደማቅ፡ግዑዝ፡ሆነችና፣
ዝም፡ብላ፡እያየችኝ፡አልገብቷት፡ሆነና፣
ልቤ፡ቀረ፡መና።
ዝም፡ብዬ፡እያየኋት፣
አንድም፡አልቀረብኋት፤
ወይም፡አልሸሸኋት፤

ባለሁበት፡ሆኜ፡ሰማትር፣ስማትር፣
እንዲሁ፡ላድር፡ነው፡ኮከቧን፡ስቆጥር።
ያቺን፡ትንሽ፡ኮከብ።
ደግሞ፡ትንሽ፡ኮከብ…አንዲት፡ት— ንሽ፡ኮከብ።

ሡረቀ፡ብርሃኗ፣
ጨረር፡ፍንጥቅታዋ፣
የህይወት፡እግቢዋ፤
የማርያም፡መቀነት፡በጭጋጉ፡ግርጃ፣
ሰው፡ምኑ፡ይዞ፡ሊቀርብ፣ለዚች፡አንዲት፡ኮከብ፣
ለእሷ፡መማለጃ።
እያደነቁ፡ዝም፣
እየተደመሙ፤
ወይ፡ፀንቶ፡እስኪገድል፣
ወይ፡ሸሮ፡እስኪጠፋ፣
የዝምታ፡ሕማሙ።
ያንዲት፡ትንሽ፡ኮከብ።

፲፱፻፸፱ ዓ.ም.



# ጉራማይሌ

እያንዳንዱ፣
ከነፍሱ፡ሌላ— ሌላ፡ነፍስን፡አርግዞ፤
ሁለተኛ፡ገፁን፡ከርእይ፡ማዶ፡አግዞ፤
ሁለት፡ ዐይነት፡ሰውነት፣—
ጉራማይሌ፡ሰው።
አንድ፡ገፁ— የሚታየው— ሲሥቅ፡ሲፍለቀለቅ፣
ሌላው፡ገፁ— ኀቡኡ— ሲታመም፡ሲጨነቅ፤
አንዱኛው፣
አንዱ፡ገፁ፣ ዱረቱን፡ነፍቶ፣
ሌላው፡ገፁ፣ የተቆለመመ፣
ቅስሙን፡ሰብሮ፣ አንገቱን፡ደፍቶ፤
አንዱ፡ፈክቶ፣ ሌላው፡ከፍቶ፤
ባንድ፡ገፁ፡ ታታሪ፣ በሌላው፡ታካች፡ቦዘንተኛ፣
ባንዱ፡ነቅቶ፡አዳሪ፣ በሌላው፡ሙሉ፡ውሎውን፡የሚኛ፤
ሁለት፡ዐይነት፡ህይወት፡
ሁለት፡ዐይነት፡ሰውነት።
አንዱ፣ አትንኩኝ፡ባይ— ኩርፍተኛ፣
አንዱ፡ሣቂ— ተጨዋች፣ መለኛ፤
አንዱ፣ ሁለመናውን፡ዘግቶ፣
አንዱ፣ ገረገራውን፡ጥሶ፣ ውስጠ፡ውስጡን፡ከፍቶ፤
አንዱ፣ ሥሥትን፡ይቃኛል— በነፈግታ፤
አንዱ፣ ተሳትፎን፡ይናኛል— በእስይታ፤

ምንነቱ፡

ሁለት፡ዐይነት፡ነው፡ህይወቱ፤
ጉራማይሌ፡ነው፡ሰውነቱ።
አንድ፡ገፁ፡የቆረጠ — ሀሞቱ፡የሆረጠ፤
ሌላው፡ገፁ — ሥጋት፤ ሥጋት፡ብቻ — የሆመጠጠ።
አንዱ፣ ቃናን፡ሽቶ፡ዙሪያውን፡ሲያጣጥም፣
ሌላው፣ ቃናው፡ጠፍቶበት — እጅ፡እጅ፡ብሎት፡
ወስፋቱ፡ሲለግም፤
አንዱ — የነፍሱን፡ወይን፣ ሊረካ፡ይጠጣል፤
ሌላው — ምች፡እንዳይመታው — ገፊቱን፡አሽትቶ፡ይመጣል።
ሁለት፡ርእይ፣
ሁለት፡ግብር፤
ጉራማይሌ፡ሰው።
አንዱ፣ ቁጭ፡ብሎ፡ሰማይን፡ይቧጥጣል፤
ሌላው — የቆመበት፡ምድር፡ርቆት፣
እንደላስቲክ፡ይለጠጣል፤
አንዱ፡ያዘግማል፣ ይቆነናል —
ከጊዜ፡ጋር፡ጠብ፡የለውም፤
ሌላው፡ይሮጣል፣ ይባዝናል —
ጊዜ፡ባላንጣውን፡አያምነውም።
ሁለት፡ዐይነት፡ህይወት፣
ባንድ፡ማኅደር — በደባልነት፤
ሁለት፡ገፅታ፤
ጉራማይሌ፡ሰው።



# ስለሚቃጠሉ!

እኔ—
ስለከዋክብቱ፡ምን፡አውቃለሁ?
ግን፡ደግሞ፣ በሥነ፡ጥበቡ፡ተመርቄያለሁ፤
በዴግሪ።
እንጂ— እኔ—
ማታ፡ማታ፡
አቤቱ፡መሀረኝ!
እንደሚል፡አንጋጥጬ፣ ሰማዩን፡ስመለከት፣
ተገልብጬ፤ ስለማያቸው፡ኮከቦች፡
ምን፡አውቃለሁ?
እኔ—
የኒያ፡ስንትስ፡ዝም፡
ቁጥራቸው፡አይታሰበኝም፤
ድምፃቸው፡ አይሰማ፤
መልካቸው፡በውብ፡አይለይ፤
ብርሃናቸው፡የኛ፡ያልሆነ—ረቂቅ፤
ሙቀታቸው፡በእቶን፡ተሠፍሮ፡የማይታወቅ።
ስለኒህ፡ከዋክብት፡ምን፡አውቃለሁ?
ግን፡ደግሞ፣ በሥነ፡ጥበቡ፡ተመርቄ፡
ዴግሪየን፡አስመርቄያለሁ።
ስለኒህ፡ከዋክብት፡ቢሉ—
ምንም፡አላውቅ፡ግና።

ብርሃናቸው፡ ይስበኛል፤
ቅዝቃዜያቸው፡ የታመቀ፡ ሙቀት፡ ሁኖ፡ አቅፎኛል፤
ዝምታቸው፡ በረጋ፡ አንደበቱ፡ ያጫውተኛል።
ሳይወጡ፡ ሲቆዩ፣ እፈልጋቸዋለሁ፤
ስም፡ ሰጥቼ፣ አንድ፡ ብዬ፡ ለመለየት፡ እመኛቸዋለሁ፤
ባልፈጃቸውም፡ ቅሉ፣
ውዬ፡ አድሬ፡ እቆጥራቸዋለሁ።
እኒህ፡ የሚናፈቁ፡ ከዋክብት፣
ልብ፡ ይሰያሉ።
በተራ፡ ቋንቋ — ዱስ፡ ይላሉ።
ለምን፡ ቢሉ፣
እንዱ፡ የማላውቀው፡ ይኼ፡ ነው — ስለከዋክብቱ።
ግን፣ ዴግሪዬንም፡ ኢስመርቄያለሁ፤
በቃህ፡ ተብዬ፣
በቃሁ፣ እሺ፡ ብዬ፣ ለመግደርደር፡ በቅቻለሁ።
ታዲያም — እኒህን፡ ከዋክብት፣
እኔ — አውቃችኋለሁ፡ ስል፡ በፈገግታ፣
ኧረ፡ የለም! አያውቁንም፡ ጌታው!
መልክ፡ አሳስተው፡ ይሆናል! ይላሉ፤
በለዘብታ።
ዐይናቸውን፡ ጭፍን፡ እያደረጉ።
ብዙ፡ ቀን፡ አይቼያቸው፣
አንድም፡ ቀን፡ ኢልለየኋቸውም።
ስለኒህ፡ ከዋክብት፡ ምን፡ ኣውቃለሁ?
ምንስ፡ ብዬ፡ ኣወራለሁ?

ለምን? እንዴት?

ስባልስ?

ላውቅ፡ብየ፡እመኛለሁ፤የዚህንም፡ጥያቄ፡መልስ።

ሆኖም፡ግን፤

ከዋክብቱን፡አሁንም፡እቆጥራቸዋለሁ፤

ባልፈጃቸውም፡ቅሉ።

በየተራ፡ተለይተው፤ ሳይነጣጠሉ፡

ከዋክብት፡ተብለው፡ይታወቁ፡ዘንድ፡ብቻ፡

እመኛለሁ።

‘ባንድ፡አጠቃሎ፡ከዋክብትን፡ማየት፤

‘የተፈጥሮን፡ኅፅን፡ልምላሜና፡ውበት፡

‘እንደጥዑም፡ወይን፡

‘ቀመስ፡አድርጎ፡አጣጥሞ፤

‘መልካም፡ሥራ፤

‘ውብ፡ ወርቅ፡ዘቦ፤’

ብየ፡ስለማወድሳቸው፡ብዙ፡ያልታወቁ፡ከዋክብት፡

ምን፡ ኣውቃለሁ?

በህዋው፡ውስጥ—በገዋው—ሞልተው፡ያድጋሉ፤

ዓለሙ፡ዓለማቱን፡ይሞላሉ፤

በመንፈሳችን፡ብርሃንን፡ይፈነጥቃሉ፤ነፍስን፡ያበራሉ፤

እጅግ፡ያበራሉ—ደግሞም፡ይሞቃሉ፡—ስለሚቃጠሉ!

ሳይቃጠሉ፡እንዳይበሩ፡ግን፡እሙን፡ብያለሁ፤

ይህችን፡ብቻ፡ተረድቻለሁ—አውቄያለሁ—አምኛለሁ!

ከዚህ፡እምነት፡በቀር፡ ምን፡ኣውቃለሁ?

ብቻ፡ በሥነ፡ጥበቡ፡ተመርቄያለሁ።

ስለከዋክብቱ፡ግን—ምንም፡አላውቅ፡ግና። 

# ዋቢያችን

ታሪክ፡ መቼም፡ አይሞትም፣
ከቶ፡ መች፡ ሙቶ፡ ያውቃልና፤
ታሪክ፡ አለፈ፡ ቢባል፣ ባናስተውለው፡ ጊዜና፣
ታሪክ፡ ሞተ'ኮ፡ አያስብልም፤ ታሪክ፡ መች፡ ሞቶ፡ ከቶ፤
ሁሉንም፡ ነገር፡ መዝግቦ፣ ያለውን፡ ሁሉ፡ አኖቶ፣
የዝጌሩን፡ ለዝጌር፡ ትቶ፣ የቋሣሩን፡ በኛ፡ ጥሎታል፤
በኛም፡ የታሪክ፡ ተግባር፡ ታሪክ፡ ለነገ፡ ይዘምታል፤
ካሬን፡ ተመርኩዞ፣
የሚጋዘውን፡ አግዞ።
በዛሬ፡ ድልድይ፡ ተሻግሮ፣
አባይ፡ ነባዩን፡ ለይቶ፣ ያላጤንነውን፡ ዘክሮ፣
ታሪክ፡ ትንቢትን፡ ይሆናል፤
ጎደመጡቱ፡ መልካም፡ ዋቢነት፡ ይቆማል፤
ለሚዘልቁቱ።
በሚሥቁበት፡ ማና፡ እየሣቀ፡ ይዘልቃል፤
ዕብሪተኞችን፡ ቢሉ፡ ይጨፈልቃል።



## ማሳረጊያ

ከእውነት፡የበለጠ፡ፀጋ
ከነፍስ፡ከሥጋ፡የተቆራኘ፡
የሰውነት፡ዜጋ፡
የለም፡ባይ፡ነኝ፤
እሁንም፡እላለሁ፡ደግሜ፤
ምን፡ቢከፋ፡ምሬቱ፤ ምን፡ቢፀና፡ሕማሜ።

ይሁን!



በግጥሞቹ፡ ውስጥ፡ አንዳንድ፡ ቃላት፡ ለአንባቢ፡ "እንግዳ"፡ ይሆናሉ፡ ብ
ዬ፡ በመገመት፡ አጭር፡ መዝገበ፡ ቃላት፡ ለመፃፍ፡ አስቤ፡ ተውኩት።
በአማርኛ፡ ተፅፈው፡ ያሉትን፡ መዝገበ፡ ቃላት፡ አገላብጦ፡ ትርጉማቸውን፡
ማግኘት፡ ይቻላልና። በተለይ፡ ግን፡ "ራእየ፡ ግምበኛ፡ ዘአራዳ፡ ጊዮርጊ
ስ"፡ የሚለው፡ ከአማርኛውና፡ ግዕዙ፡ "ተዳቅለው"፡ የሚገኙበት፡ ስለ
ሆነ፡ የግጥሙን፡ "ትርጉም"፡ ለመረዳት፡ ፍንጭ፡ ይሆን፡ ዘንድ፡ ግዕዙ፡
እንግዳ፡ ወይም፡ ባዕድ፡ ለሆኑባችሁ፡ የግዕዝን፡ ቃላት/ሐረጎች፡ ፍቺ፡
ከዚህ፡ በታች፡ አሠፍራለሁ። ግጥሙ፡ ገጽ፡ 29-30 ላይ፡ ነው።

ራእየ፡ ግምበኛ፡ ዘአራዳ፡ ጊዮርጊስ

የአራዳ፡ ጊዮርጊስ፡ ግምበኛ፡ ራእይ

ራእይ = ሕልም፡ (በእንግሊዝኛው፡ vision ወደሚለው ይጠጋል፤ በመጽሐፍ፡ ቅዱስ፡ 'revelation')

ግዘፍ = ሥጋ፤ አካል

ህልውና = ሁነታ፤ ኑሮ፤ አኗኗር

ኅሩያን፡ በህልውናሆሙ = በሁነታቸው፤ በኑሯቸው፡ የተመረጡ፡

ፃድቃን፡ በሕገጋቴሆሙ = በሕጋቸው፡ የፀደቁ፤ በውስጠ፡ ወይራ፡ አነጋገር፡ ወይም፡ በመሣለቅ፡ ዲይነት፡ በሕ ጋቸው፡ "እውነተኞች፡ የሆኑ" (ሲፈርዱ፡ እንደማ ለትን)

ልፅሉፅ፡ ከመ፡ መዳልው፡ በፍትሖሙ = ፍትሕ፡ ሲሰጡ፡ የማ ያዛቡ፤ ርቱእ፡ የሆኑ። (ሥላቅ)

ልፀሉፅ = የተባ፤ ትክክል፡ የሆነ፤ ልስልስ፡

መዳልው = ከወርቅ፡ ሚዛን፡ ላይ፡ እንደሰንበሌታ፡ ወይም፡ ሰይፍ፡ ሆኖ፡ ቀልቀል፡ የሚ ወርድ፡ የሚዛኑን፡ ትክክለኛነት፡ የ ሚያሳይ

ዘኅረዩ፡ አርእስቲሆሙ = (ቃል፡ በቃል) ራሳቸው
ን፡ የመረጡ፡ የሾሙ፤ በአገባቡ፡
ራሳቸውን፡ የመረጡ

ትሩፋት፤ ጊድራት = ምዕዋቶች፤ ለነፍስ፡ ተገቢ፡ ለ
ዲሁ፡ የሚሆን፡

ለበዊ = ልብ፡ ያለው፤ የሚስተውል፤ የሚያስብ፡
ነባቢ = አስቦ፡ የሚናገር፡
ገባሪ = ሰሪ፤ ፈጣሪ
(በሃይማኖት፤ የሰው፡ ነፍስ፡ ባሕርያት
ለበዊነት፤ ነባቢነት፤ ሕያውነት፡ ናቸው፤
እዚህ፡ ሕያውነት፡ ገባሪነት፡ በሚለው
ፅንስ፡ ሐሳብ፡ ተተክቷል)

ሕገ፡ ኅሩያን = የምርጦች፡ ሕግ፡

በኅዳጣን፡ ጠገብ = በጥቂቶች፡ ጸሠር (የበኅዳጣኖችን፡
የተገዢነትን፡ ጥጥ፡ ይጠቅሳል፡)

መለኮት = የአምላክነት፡ ባሕርይ

ሰብእና = ሰውነት — የሰውነት፡ ባሕርይ

ይህ፡ ግጥም፡ "ሙክራዊ"፡ ነው፡፡ ሰፋ፡ ባለ፡ አገባቡ፡ እንግሊዝኛው፡
"ኤክስፐርሚንታል"፡ ከሚለው፡ ይመደባል፡ የአማርኛውና፡ የግዕ
ዙ፡ መደባለቅ፡ ለቁንጅና፡ ወይም፡ ለጌጥ፡ የተደረገ፡ ሳይሆን፡ ምክ
ንያት፡ አለው፡፡ የግዕዙ፡ ባማርኛ፡ ተተርጉሞ፡ ቢቀር፡ ከቻለውን፡
ሚዛን፡ እያነሣም፡፡ የኅብር/የምርምር፡ ጣጣ፡ ነው፡፡ በዚህ፡ አገባ
ባቸው፡ ቃላት/ሐረጎች፡ እንደ ሰይፍ፡ ሁለት፡ ወገን፡ ሥለት፡ አላቸው፡፡

መግቢያ

በዚች፡ ትንሽ፡ መድበል፡ ውስጥ፡ የሠፈሩት፡ ግጥሞች፡ ከ ፲፱፻፷ ዓ.ም. ጀምሮ፡ በተለያየ፡ ጊዜ፡ የተገጠሙ፡ ናቸው። ከነዚህ ውስጥ፡ ጥቂቶቹ፡ ከተወለዱ፡ በኋላ፡ ታርቀቀዋል፤ ተቀጥተዋል። አንዳንዶቹ፡ ደግሞ፡ አፍታዊ፡ ግፊት፤ አለያም፡ ያንድ፡ አፍታ፡ ተመስጦ (ኢንስፒሬሽን) እንደፈለቃቸው፡ የተጻፉ፡ ናቸው። ይህ፡ ስለተገለ፡ግን፡ ለቅዱስ፡ ያሬድ፡ የዜማ፡ ሥልቶቹን፡ ያፈለቁለት፡ አዕዋፍ፡ ከእኔ፡ ጋር፡ መኅበር፡ ውለው፤ ወይም፡ በነሱ፡ የተመሰለው፡ መለኮታዊ፡ ኪን፡ በኔም፡ አድሮ፡ በደመ፡ነፍስ፡ ያናገረኝ፡ ቃላት፡ ናቸው፡ ማለት፡ አይደለም። በሰሎሞን፡ ዴሬሣ፡ የ"ልጅነት"፡ ቋንቋ፡ እምቢ፡ ባለው፡ ፈንቅለው፡ የወጡ፡ ናቸው። "የስሜት፡ ንዋሬዎች" በሚል፡ አጠቃላይ፡ ርእስ፡ ሥር፡ ያለአርእስት፡ የቀረቡት፡ ግጥሞች፡ የዚህ፡ አፍታዊ፡ ግፊት፡ ምሳሌ፡ ሁነው፡ ሊታዩ፡ ይችላሉ። ለሁሉም፡ ቢሆን፡ ግን፡ ለግፊቱ፡ ምክንያት፡ የሆኑት፡ ነገሮች፤ ሁኔታዎች፤ ወይም፡ ሀሳቦች፡ ከዚሁ፡ ካለንበት፡ ምድር፡ ያሉ፡ ናቸው። አፍታዊነታቸው፡ በእእምሮ፡ ተፀንሰው፡ ከብዕር፡ የፈለቁበትን፡ ከወረቀት፡ መስክ፡ የደረሱበትን፤ ሥጋ፡ የለበሱበትን፤ አንደበት፡ የገዙበትን፡ ሁኔታና፡ ፍጥነት፡ የሚያመለክት፡ ነው። አንዳንዶቹ፤ በተለይ፡ ግን፡ "ያንድ፡ አዝማሪ፡ ዘፈን"፡ እና፡ "አዲስ፡ ግጥም"፤ ይሁነኝ፡ ተብሎ፡ ለሙከራ፡ ያህል፡ ከተነደፉ፡ በኋላ፡ የታሹ፡ ናቸው፡— ያመረቃሉ፡ አያመረቁም፡ የሚለውን ለአንባቢ፡ እንጂ፡ እተዋለሁ።

ለመሆኑ፡ ግጥሞቹ፡ ስለምንድን፡ ናቸው፡ የሚል፡ ጥያቄ፡ (በተለይ፡ ስለአንድ፡ ሁለቱ) መነሣቱ፡ አይቀርም። ብዬ፡ ልገምትና፡ "እንኳገባችሁ፡ ደረሱበት" ብዬ፡ ብመልስ፡ ቅር፡ አትሰኙ፡ አደራ! ጥያቄውን፡ ማቃለል፣ ወይም፡ ሊመለስ፡ የማይችል፡ ጥያቄን፡ በብልጣ— ብልጥነት፡ ባቋራጩ፡ ለማምለጥ፡ የተደረገ፣ ወይም፡ የምሁራዊ፡ ንቀት ወይም፡ ትዕቢት፡ ጉዳይ፡ አይደለም። ተገቢው፡ መልስ፡ ይኸው፡ ብቻ ስለሆነ፡ ነው — ቢያንስ፡ በዚህ፡ ሁኔታ! የዚህ፣ በእርግጥም፡ እንደየ ሁኔታው፡ ተገቢነት፡ ያለው፡ ጥያቄ፡ መልስ፡ ከግጥሞቹ፡ ከራሳቸው፡ ብሎም፡ ከአንባቢ (አንባቢ፡ ካገኙ) የትርጓሜ፡ ዓይነት፡ ተፈልፍሎ፡ ይገኝ፡ ዘንድ፡ የግጥም፡ ጥበብ (ባጠቃላይም፡ የሥነ፡ ፅሑፍ፡ ጥበብ) ግድ፡ የሚለው፡ ነገር፡ ነው።

ግጥሞቹን፡ አንብቦ፡ ትርጓሜ፡ የመስጠት፡ ነገር፡ ቁም፡ ነገር፡ እንዳለው፡ ጨዋታ፡ ነው። ሽምብራ፡ ጠርጥሮ፣ ገቈሳ፡ ፈልፍሎ፡ መብላት፡ እርካታው፡ እሁለቱ፡ ላይ፡ ነው — አንድም፡ በልቶ፡ ረሀብን፡ ማስታገሱ፡ ወይም፡ መኛገሉ፡ እለ፤ አንድም፡ መፈልፈሉ፡ ጥበብን፡ የሚጠይቅ፡ ጨዋታ፡ መምሰሉ፡ ነው። በግጥሞቹ፡ ውስጥ፡ ሊኖር፡ የሚችለውን፡ ትርጉም፡ ፈልፍሎም፡ ይሁን፡ ጠርጥሮ፡ ማውጣት፣ የተገኘውንም፡ ፍሬ ነገር፡ አኝምጦ፡ ማጣጣሙ፡— ማለትም፣ ጥያቄውን፡ እንሥቶ፡ ለመመለስ፡ አስተዋፅኦ፡ ማድረጉ፡— የአንባቢ፡ ፈንታ፡ ነው። ይህ፡ እኔንም፡ ይጨምራል፤ ምነው፡ ቢሉ፡ ግጥሞቹን፡ አሁን፡ የማይበት፡ አንፃር፡ ሲፀነሱና፡ ሲፃፉ፡ ከነበርኩበት፡ አንፃር፡ ትንሽም፡ ቢሆን፡ የተለየ፡ ነውና። እና፡ ሁሉም፡ እንደ፡ ብስሉ፣ እንደ፡ ክበቱ፡ ያደርጋቸው፡ ዘንድ፡ ነፃ፡ ነው።

ይህ፡ ስለተባለ፡ ግን፡ ሁሉም፡ እንዳሻው፣ የፈለገውን፡ እየከተተ፣ ነገሩን፡ መልክ፡ ያለመልኩ፡ እያሳቆጠ፡ ጠቅልሎ፡ ይቀጠው፡ ማለት፡ አይ

ዲሰም። ከግጥሞቹ፡ ይዞታ፣ ከቃላቱ፡ አሰካክና፡ አገባብ፡ ውጭ፡ ትርጉም
መጨመር፡ ነገሩን፡ መደረት፡ ይሆናል። እንዲያም፣ እንዲት፡ ቃል፡ ነጥሎ፡
በዓለም፡ ላይ፡ ሊኖራት፡ የሚችለውን፡ ትርጉም፡ እያሸተቱ፡ ለማስተንተ
ን፡ መሞከሩ፡ የቁንጫ፡ መለካጫ፡ ማውጣት (ወይም፡ "ፀጉር፡ መሰን
ጠቅ፡") ይሆንና፡ አንባቢና፡ ግጥም፡ ተለያይተው፡ ይቀራሉ። የአንባቢ፣
የተርጓሚ፡ ነፃነት፡ በግጥሞቹ፡ ክበብ፡ የተገደበ፡ ነው። የቃላት፡ አገ
ባብ፣ የሐረግ፡ አሰካክ፣ የስንኞች፡ ቅደም፡ ተከተል፣ ይህና፡ ሌላ፡ ሌላም፡
የግጥም፡ ሥልት፡ ለምንሰጠው፡ ትርጓሜ፡ ፍንጭ፡ ሰጪ፡ ወይም፡ ፋና፡ ጎ
ብሪ፡ ሊሆን፡ ይችላል።

በግጥም፡ ዓለም፡ ምላጭ፡ ሲያብጥ፡ ውሀ፡ ሲያንቅ፡ ሰምተን፡
እናውቃለን። በግጥም፡ ዓለም፡ ፍየል፡ ዐይኗን፡ ሲያማት፡ ነገር፡ እንጂ፡
ነው፡ እሱ፡ የሚያከማት። በዚህ፡ ልዩ፡ ዓለም፡ ድንጊያ፡ ደም፡ አልቅሶ፡
ውሾ፡ እሱን፡ ልሶ፡ ሲኖሩ፡ እናያለን። በዚህ፡ በምናውቀው፡ እንግዳ፡ ዓ
ለም፡ የተፈጥሮ፡ አክሄድ፡

... ፍጥነቱ፣ እንደዔሊ፡ ሲወረወር
እንደ፡ [እግሯ]፡ ተነሥቶ፡ እስኪያርፍ፡
ያልፋሉ፡ ሺህ፡ ዘመናት*

በዚች፡ መድበል፡ ውስጥም፡ አምሳያን፡ ሰድቦ፡ ማስለቀስ፡ ታገኛላችሁ፣
በጊዜ፡ ላይ፡ ተፈቶ፡ የሚሆነውን፡ ታያላችሁ፣ ከመሬት፡ ቁጣ፡ ቀጥቆጠ፣
ከውሀ፡ ቅቤ፡ ንጦ፡ አቅልጦ፡ መርካቱን፡ ትታደሳላችሁ። ገጣሚው፣ ቃላት፡
ልዩ፡ ኃይል፡ አላቸው። የዘወትሩን፡ እንግዳ፣ አሮጌውን፡ አዲስ፡ ያደርጋ
ሉ። የተበታተነውን፡ ይሰበስባሉ፣ አጥንቱን፡ ሥጋ፡ ያለብሳሉ፣ በበድኑ፡ የሞ
ቀ፡ እስትንፋስ፡ ለቀው፡ ነፍስ፡ ይዘራሉ። እንደሁኔታው፣ ዘለዓለማዊ፡

* ከበደ፡ ካሣ፣ "ተፈጥሮ"፡ በሚል፡ ግጥሙ፡ ካሠፈራቸው፡ መሠመሮች፡ የተጠቀሰ።

ህይወትን፡ ይሰጣሉ፤ ወይም፡ እመቀመቅ፡ ያወርዷሉ። በሥነ፡ ፅሑፍ፣ ዓለም፡ ቃላት፡ ሁሉን፡ ቻይ፤ ሁሉን፡ አድራጊ፡ ናቸው። በዚህ፡ ልዩ፡ ዓለም፡ አልፋና፡ ኦሜጋው፡ እነሱው፡ እንጂ፡ ናቸው — ሁሉም፡ ሊያልፍ፣ የሚቀሩ!

የመጀመርያ፡ ትምህርታችን፡ ከዚህ፡ ላይ፡ ሆኖ፡ ሌላውን፡ ሁሉ፡ ከዚህ፡ ጋር፡ አያይዘን፡ እንመልከተው። በተረፈ፡ ይህችን፡ ትሑት፡ የፅሑፍ፡ መድበል፡ አንባቢ፡ የመውደድም፡ ሆነ፡ የመጥላት፡ ጉዳይ፡ የየግላችን፡ ሲሆን (ከያኔ፡ የማልሰጥበት፡ ነገር፡ ላውና)፤ ብቻ፤ ውዴታም፡ የግዴ፡ ፍቅር፡ ግላቸውም፡ የእልህ፡ እንዳይሆን፡ አደራ!

የ. አ

ሎስ፡ አንጀለስ

## የአዋቂ፡ጥያቄ

በዝምታ፡ከንፈር፡ሞጦ — ወይ፡በጩኸት፡ዐይን፡አፍጥጦ፤
ችላ፡ማለት፣ መታባቱ — ወይ፡ተናጅ፡መደንፋቱ፤
ግራን፡መስጠት፡ቀኝ፡ሲመታ፣
ወይ፡አፀፋውን፡መመለስ፡እንዳፍታ፤
መታነቁ፣ ወይ፡ማነቁ፣
ወይም፣ ነገርን፡መተው፡መናቁ፤
መለዘቡ — መሻከሩ፣
መቮርበሩ፣ ወይም፡ደግሞ፡መበርበሩ፤
በንቃግ፡ዘንድ፡መባዘቱ — ወይም፣ሲያጡ፡ገድሎ፡መሞቱ
ለጦር፡ሂዱ፡መዋጋቱ፣ ወይ፡መሸሹ፤
ንፁህ፡መስሎ፡መታየቱ፣መቆሸሹ፤
ቀኑ፡ሲመሽ፣ ነጋ፡ጠባ፣
ምርጫው፡ሁሉ፣ በየፈርጁ፡ካልቀረበ፡ካልተጠና፣
ህልውና፡ምን፡ሊፀና!

●

## ያላዋቂ፡መልስ

አይ፡ወዳጄ!
ቢከፋህ፣ ዝም፡ብለህ — አፍህን፡ተለጉመህ፣
ቀኝ፡ቢሉህ፣ ግራ፡መልሰህ — አንድ፡ሁለት፡ጥፊ፡ተልሰህ፤
ብርዝ፡ሲወጣህ፡ስጣፍጥ — ሰፈፍ፡ወጥቶልህ፡ስትቀልጥ፣
ሰም፡ተጨፍልቀህ፡ስትጧፍ፣
ይተክሉህና፡ከመቅረዝ፣

ይለኩሱሃል፡ያበሩሃል፤
በፋናህ፡ዞሪያ፡ከበሮ፡ይደልቁልሃል።
ታፀድቃለህ፡ታማልድ!
ከዚህ፡ኑሮ፡ምን፡ሊገድ!

አየህ!
አገል፡ብለህ፡ስትሄድ—ያየ፡ቢጠቁም፡ከመንገድ፣
ንስሐ፡ገብተህ፣ማረኝ፡ብለህ፣
ማቅህን፡ለብሰህ፡ዐመድ፡ቅመህ፣
እንድትመስል፡እህዮን፣
በግብር፡ወንድምህን።
ታፀድቅ፡እንጂ፡ታማልድ!
ታፀድቅ፡እንጂ፡ታማልድ!
ከዚህ፡ኑሮ፡ምን፡ሊገድ!

፲፱፻፶፫ ዓ.ም.



ተናጋሪ፡ጠፍቶ?

(ወይም፣ የሥጋ፡ጥያቄ)

መች፡ጨነቀኝና፡የናንተ፡ልፍለፋ፣
በናንተ፡ልፍለፋ፡
ንብረቴ፡ላይፋፋ።
ትዳሬስ፡ካልሞላ፡ምንስ፡ዶለኝና፣
ዕድሜ፡እለምናለሁ፡ህይወት፡ጣፍጦኝና!
ህይወቱ፡ካልሞቀኝ፡ካልቆሰቆስኩቱ፣
መቃብር፡እማይበጅ፡ከመኮራመቱ።
ቢከፋም፡ተረቱ።

ምን፡ጡር፡ይሆንብኝ፡
አለመጠየቄ፡የራሴን፡ኅሊና፤
አለመጣጠኔ፡የራሴን፡ልቡና!
ምንኝ፡ጡር፡እሠራ!

ምንኝ፡ጡር፡እሠራ —
ባማትሮ፡ብቻ፡አልፌው፡ብሄድ፡
በሰውነቴ፡ውስጥ፡የማየውን፡ጉድ!
ከሰውነቴም፡ውጭ —
ሲያፈጥብኝ፡ውሎ፡
እፍጦ፡’ሚያሳድር፣

በውን፡ የሚያቃዠኝ፡ የሚያባንነኝ፣
ብዙ፡ ታሪክ፡ አለ፡—
ሰሚ፡ ሰው፡ ቢገኝ።
ብዙ፡ ታሪክ፡ አለ፤ ብዙ — ብ — ዙ፡ ጉድ፤
ጉድ፡ አልዘረዝርም — ፍጁታው፡ የናንተ!
ማዳመጥ፡ አልበቃም፡ ላልተመለከተ፤
ተቅማጥ፡ በላው፡ ሲባል፡ ብዙ፡ ያመረተን፣ ብዙ፡ የከተተ!

ጥንታቱ፡ ሲያወሩ፡
ታሪክ፡ ሲቀፅሉ፣
አዝመራ፡ ሲሰምር፡
በሽታ፡ ነው፡ አሉ!

ሲባል፡ እንሰማለን።
እኛስ፡ ምን፡ አድምጠን፡ ምንድን፡ እናያለን?
ይህን፡ ታምር፡ ንግር፡
በማንስ፡ እንደበት፣ በየትኛው፡ ቋንቋችን፡
እንተረጉማለን?

፲፱፻፷፫ ዓ.ም.

## አስታራቂ፡ጠፍቶ

አምላክን፡ ሰድቤው፣
በጣም፡ ተበሳጭቶ፣
ከኔ፡ጋር፡ ማውራቱን፡ፈጠመና፡አብቅቶ፣
ቅር፡እንዳለው፡ሄዴ፤
ዞር፡ብሎም፡ አላየ ፡፡
ሄደ፡ ገሰገሰ፣
በስድቤ፡ተነክቶ፣ልቡ፡እያለቀሰ፡፡
ለናቱ፡ነገረ፣ እንድትገሥፀኝ—
ፍርድን፡ያውቃልና፤
ግና፡ ሁኖ፡ አልሆነም፣
ከእመቤቴም፡ጋራ፡ተጣልተናልና፡፡

፲፱፻፳፫ ዓ.ም.



# መዝሙር፡ዘሀበሻ

ምን፡አምኖ፡ይኑር፡ሰው፡ሁላ፣
እረ፡ምን፡አምኖ፤
የጥፋት፡አክሊል፡ከራሱ፡ጭኖ፤
እረ፡ምን፡አምኖ።
ምን፡በልቶ፡ይኑር፡ሰው፡ሁላ፣
እረ፡ምን፡በልቶ፤
እህል፡ሳይጠፋ፡አቁን፡ተዘግቶ፤
እረ፡ምን፡በልቶ።
ምን፡ይዞ፡ይጓዝ፡ትስብእት፣
እረ፡ምን፡ይዞ፤
ዘመን፡አመጣሽ፡እስከነነፍሱ፡ተግዞ፤
እረ፡ምን፡ይዞ።
ምን፡ብሎ፡ይሙት፡ሰው፡ሁላ፣
እረ፡ምን፡ብሎ፤
የሰው፡ባልሆነው፡ስድስ' ክንድ፡ዐፈር፡ተከልክሎ፤
እረ፡ምን፡ብሎ።
ምንን፡ንስሐ፡ይግባ፡ሀበሻ፤
ምኑንስ፡ይይዝ፡ሱባኤ፤
ሲወሰንበት፡ጦም፡ጦለቱ፡በባይተዋሮች፡ጉባኤ።

፲፱፻፺፫ ዓ.ም

ያንድ፡አፍታ፡ሽርሽር (ወይም፡የቂል፡ዘፈን)

ፈገግታዋ፡የደስታ፡አይደለም።
ኩርፊያዋም፡የቁጣ።
የንዴት — የመሰደብ፡እንጂ!
መከለሻው — 'አንቺ፡ቀቱ!'— ሲጨመርበት፣
ቁጣዋ፡ይከሰታል፣ በደነዘዘ፡ፈገግታ፤
ጆሮዋን፡እንዲህ፡ላለ፡ቅሌት፡ዘግታ።

እንደኮምፒዩተር፣ እንደሞሉት።

እንደኮምፒዩተር፣ እንደሞሉት፣
እንዷ፡ታልፋለች፡ባጠገቤ፤
ከጐኗ፡ልጇን፡አሚቅላ፣
ካናቷ፡ቅርጫት፡ነገር፡ተክላ፣
በሁለት፡እጇ፡ቋጫ፡መሳቦ፡እንጠልጥላ።

ፈገግታዋም፡የማሰነ።

ቅርጫቱ፡አይወድቅም — ያስደንቃል!
ጥበብ፡ነው — ኪነት፡ያለው!

ተብሎ፣
ሸራ፡ተወጥሮ፣ ቀለም፡ተቀላቅሎ፣
ምስሏ፡ይቀረፃል፡አምሮና፡አሽብርቆ።

የቆቱ፡ቆንጆ!

ይባላል።

አንቺ፡የቆቱ፡ቆንጆ!
ምስልሽ፡በሠላሳ፡ሣንቲም፡ተሸጦ፣
ቴምብር፡መሳይ፡ተለጥፎበት፡
ዓለሙን፡ይዞራል፤
ሥጋሽ፡ቤቱ፣ ካለበት፡ተገትሯል።
ምስልሽ፡ነው፡የሚሄድ፣ እስካሁንም፡የዘለቀ፤
ሥጋሽ—ሥጋሽ፡ካለበት፡ደርቆ፡ብዙም፡አልሄደ፤
ብዙም፡አልራቀ።

እንደኮምፒዩተር፣ እንደሞሉት፡
እንደሞሉት፡
እንደሞሉት።

አዎ፣ መቼስ፡ይሁና!
እግዜርሽ፡የሰጠሽ፡ውበት—ይህ፡የተፈጥሮ፡ቁንጅና፣
ስንቱን፡ሰዓሊ፡አስጠርቶ፣ —በዝና!
ስንት፡ሺህ፡ብሮች፡አፍርቶ—በቁና!
ተሸጠ።
ዳግሞ፣ እንደቆምሽበት፡መሬት፣ በካሬ፡ሜትር፡አይለካም፤
በጋት—በሥንዝር፡ብቻ!
እንዳንቺም፡መሬት፡ጥጉን፡ጥሎ
በሩብ፡በሸልንግ፡የተገዛ፡ሳይሆን፣

ሊቃውንት፡የሚሻሙበት፣
የቁንጫ፡መላላጫ፡የሚወጣበት — ጥበብ፡ሆኗል፤
ለጉድ፡ለታምር፡ይታያል!

ግሩም፡እንጂ፣ግሩም፡አይደል!
አየህ፡ቅርጫቱን፡እንዴት፡እንደተሸከመች!
ደግሞ፡በጀርባዋ፡አንዲት፡ትንሽ፡ቆቱ፡
አዝላለች!
በሁለት፡እጇ፡ጮጮ፡መሳይ፡ይዛለች!
አይከብዳትም!አይደክማትም!
አቤት፡ይቺ፡ለማጥም!

ተብሎ፣
ከንፈር፡ይመጠጣል፡ዐይኖች፡እየሣቁ፣
ያንቺን፡ምስል፡ከበው፡ሊቆች፡ሲደነቁ፡፡

መልሺላቸው፡እስቲ — አንቺ፡ምስል፣አንቺ፡ቆንጆ ¡
ሥጋ፡ለብሰሻል — የሚደክም፡የሚያመው ¡?
ትበያለሽ — ወይስ፣እህልም፡ትተሻል ¡?
ጉንሽ፡ደረቅ፡ነው — ተመችቶሻል ¡?
ቁጣሽ፡የምር፡ነው ¡? ፈገግታሽስ — የደስታ ¡?
ያን፡ሁሉ፡መንገድ፡ስትቆርጪ፣
'ትርኪምርኪውን'፡ስትሸጪ፤

እጅሽ፡ጭነት፡፡

ራስሽ፡ጭነት ።

(እኖንትሽ፡ብቻ፡የለው፡ጭነት)

ሀብትሽን፡ባንዲት፡ስሙኒ፡ለማበርከት፣
እንዲያ፡ስትሄጂ፡አይደክምሽም ፧
እውነት፡ታስገርሚያለሽ ፧
ወይስ — እውነት፡መልክሽ፡በቅቶሽ፣
ለሽራ፡ምስል፣
ላንዲት፡የወረቀት፡ቍንፅል፡በቅተሽ፤
ደስ፡ብሎሽ፡ትኖሪያለሽ ፧
ለዚህ፡ይሆን፡ሁሌ፡ፈገግታሽ፡የማይጠፋ፡
እየማሰነ፡ብቻ፡የሚሄድ ፧
እየማሰነ — እየማሰነ — እ-የ-ማ-ሰነ !

አዎ! ቱሪስቶች፡ይወዱሻል፤
የደስታ፡ምንጭ፡ነሽና!
እኔም፡ገጠምኩልሽ
(ወይስ፡ገጠምኩብሽ?)
ቅኔ፡ዘረፍኩልሽ
(ወይስ፡ዘረፍኩብሽ?)
ወይስ —
ፈገግታሽ፡ጥላ፡ሁኖ፣ ግርጃ፡ሁኖ፣
ንዴትሽን፡ሸፍኖ፣
በትዝብት፡ተጠይቂ፡ይሆን
በዚያ፡በማናውቀው፡ቋንቋሽ፤
በዚያ፡በደነዘዘ፡ፈገግታሽ ?

ትጠይቂ፡ ይሆን ?
እንዲህ፡ ብለሽ — ንዴትሽን፡ ሸፍነሽ ፤
    ‘አይሰለቻችሁ፡ ይሆን፡ እናንተ፡
    ‘በኔ፡ ዘላለም፡ መገረሙ
    ‘እኔን፡ ዘላለም፡ ማድነቁ
    ‘እኔን፡ ዘላለም፡ መመልከቱ ?’

ይህ፡ ይሆን፡ ምሥጢሩ፡— የፈገግታሽ ?
እየማሰነ፡ ቢሄድም ፣
በዱም፡ በሥጋ፡ የተዋሀደሽ ?

ሀረማያ ፤ ሰኔ ፣ ፲፱፻፶፬ ዓ.ም.

●

# ታሪክ

እኛና፡እኔ፡ዱሮ፡ጥንት፣
ወትሮ፡ሲኖሩ፡ባንድ፡ቤት፣
ያስቀኑ፡ነበር፤ ለጋ፡ቢሆኑም፡ቀንበጥ፤
በስምለምነት፡ዘመናቸው።
ቁም፡ነገሩም፡ ይኼው፡ነበር — አብረው፡ባንድ፡ላይ፡መኖራቸው።

እኛ፡እኔነትን፡አቅፎ፡ደግፎ፣
እኔ፡በኛ፡ውስጥ፡እፎይ፡ብሎ፡አርፎ፡
እንዳይኖር፣ የሚጠናወት፡ታሪክ፡መጣ፤
የእኛና፡የእኔ፡አንድነታቸው፡ላንዳፍታም፡ቢሆን፡ቅጡን፡ሊያጣ፡

እኔ፡እኛን፡ሰምቶ፡ሲኖሩ፣
እኛም፡እኔን፡ሹሞ፡ሲኖሩ፣ አንድነት፡ሰፍኖ፡በምድሩ፤
ኀሊና፡ድንገት፡አቀንቅኖ፡አእምሮ፡ድንገት፡ቢፈነድቅ፣
እኔ፡በዚህ፡ሁሉ፡መከሰት፣
ከኛ፡ፈጠረ፡ልዩነት።
እኛን፡ሊገዛው፡አሰበ፣ ዘዴ፡አቀላጥፎም፡ፈጠረ።
ዘዴው፡ተፈጥሮ፡እኔነት፣ እፎይ፡ገዛሁ፡ሲል፣በድንገት፣
እኛነት፡በርቆ፡በመንፈሱ፣
እኔን፡ቀስቅሶ፡ከትራሱ፣
ያባንን፡ጀመር፡ያቃዠው፤
በሱው፡በራሱ፡ዘዴ፡ገብቶ፣ እሱው፡ራሱ፡በቃኘው።

እናም፤
አሙ፡ዛቷ፡ ዕለት፤
እኔነት፡ባኖ፡ድንገት፡ጠፋ፤
እኛነት፡ደባሞ — እነደኞኁቱ፤ በእኔነት፡ዐፀድ፡ለምልሞ፤
እንደመቅድሙ፡ሊፋፋ ።

መጋቢት፤ ፲፱፻፷፬ ዓ.ም.



# አመፅ

የረሀብ፡እሥረኞች፡እጃችሁ፡ይፈታ፤
'እሱ፡ያቃል!' ብላችሁ፡ልባችሁ፡አያመንታ።
ማወቁን፡እንደሆን፡እግዜሩም፡ትቶታል፤
ሙታን፡አመፁና፡ከነሱ፡ይሟገታል።

ወሬ፡ከሻታችሁ፡እኔኮ፡አዳምጡኝ።
ከሙታኑ፡ዓለም፡እንደደረሰኝ፣
አምፀው፡የተነሱት፡የቆሀኑ፡ናቸው።
በምድር፡ባሉ፡ጊዜ፡የሰሙት፡ተስፋቸው፣
ከአርያም፡ሲወጡ፡ስላልሞላላቸው፣
በጥሞና፡እንዳይሆን፡በድናቸው፡ሰማና፣
ብድግ፡ብሎ፡አመጠ፡ነፍሱን፡ነጠቀና።

ግንቦት፣ ፲፱፻፷፩ ዓ.ም

## ያንድ፡አዝማሪ፡ዘፈን



አንቺን፡አይቼ፣
አንቺን፡በአእምሮየ፡ፀንሼ፣
እንደመንፈስ፡ሠርፀሽ፡በልቡናየ፡ስትከሰች፤
ልቤ፡ማኅደር፡ሁኖ፡ለኅብረ፡ቀለምሽ፡ሳስቶ፣
በስስ፡ልቤ፡ውስጥ፡ረቂቅ፡ፍቅር፡ተንሠራፍቶ፣
መንፈሴ፡በነፃነት፡ታብቶ፣ ግዘፌም፡መሬትን፡ሊለቅ፡ተነሥቶ፣
በ'ንዲህ፡ሁኔታ፡በጨረቃ፡ተመልክቶ፣
(በጨቅላነት፡ዘመኔ፡ስለማለት)
በልቡናየ—በልቤ—በሠራ፡አካላቴ፡
ልወድሽ፣ ነበር፡ቃል፡ገብቼ፤ አፍታ፡ሳልል፡ዱቂቃ።

ታዲያ—ድንገት፡ታዲያ፡ፀሀይ፡ሠርቃ፡
ዐይኔ፡ተከፍቶ፡የኅሊና፡የተኛ፡ልቤ፡ሲነቃ፤
ፀሀይ—ፀሀይ፡ቃጠሎ፡ያደበዘዘው፡መልክሽ፣
በጨረቃ፡በምሽት፡ትናንት፡ያየሁት፡ኅብርሽ፣
ቀለም፡ብቻ፡ሆነብኝ፡የተለያየ፤
ጨርቅ፡ብቻ፡ሆንሽብኝ፤
ንፉስ፡በሞፌ፡የሚመታሽ።
ዛሬን፡ሳይሽ፡በፀሀይ
(በውርዝውና፡ዘመኔ)
ሳይሽ፡ዛሬ፡በንፉስ፡ውስጥ፡ባየር፡ብቻ፡ስትረግቢ፣
ዛሬን፡ሳይሽ፡አትኩሬ፣ በፀሀዩ፣

ሳይሆን፡በዱመና፣
መንፈሴ፡ሸፈተ፡መና፡ሆንሽበትና።
ዛሬን፡ሳይሽ፡አተኩሬ፣
በፀሀዩ፣በጠራራ፤
አንቺ፡ባንዲራ!
አንቺ፡ተውለብላቢ፡ጨርቅ!
አለ፣ አንድ፡አዝማሪ።

ግንቦት፣ ፲፱፻፷፭ ዓ.ም.



## ሀሩን፡ አልራሺድ

ከዕለታት፡ባንደኛው፣ ሀሩን፡ አ‌ራሺድ፡
ከቤተ፡ መንግሥቱ፣
መጽሐፍ፡ሲያገላብጥ፡ልቡ፡ተመሥጦ፣
ዙሪያው፡ ፀጥ፡ ብሎ፡ በሐሳብ፡ ተውጦ፣
ከገጣሞች፡ አንዱ፣ ከከያኒዎቹ፣ ከብዙቹ፡መሀል፣
ያሠፈረውን፡ ቃል፣
እንዲህ፡ ሲል፡ ጀመረ፡፡

ከወዴት፡ ደረሱ፧ ከምን፡ ጋር፡ ነፈሱ፧
እኒያ፡ ሁል፡ ነገሥታት፡ ’ርኩስ፡ ከቅዱሱ፧
እኒያ፡ ሥልጣናቱ፧
ዓለምን፡ ጨብጠው፡ ሕዝቡን፡ የገዙቱ፣
ባርያ፡ ያስነዱቱ፧
እኒያ፡ መኳንንቱ፣ አንድም፡ ወይዛዝርቱ፡፡
ከወዴት፡ ደረሱ፧ ከምን፡ ጋር፡ ነፈሱ?

ኤለና፡— እንዲህ፡ ሲል፡ ቀፀለ፡፡

ከነምገሳቸው፣ ከነዘውዳቸው፣
ከነማ’ርጋቸው፣ ደግሞም፡ ከክብራቸው፣
ጎዳናን፡ ሊደዋል፡ የሩቅ፡ ሀገር፡ ሊደት፧
አንተም፡ ወዳጄ፡ ሆይ፡ ከማትቀርበት፡፡
ዓለምን፡ ፈልገህ፡ ዓለምን፡ የመረጥክ፣
የምትሰጥህን፣
ብስል፡ ጥሬ፡ ሳትል፣ ሁሉንም፡ ያካበትክ፣

ዓለምን፡ ያፈቀርክ፤ ዓለም፡ የምትሻ፤
የምትሰጥህን፡ ውሰድ፤ አታመንታ!
ታዲያ፡ ግን፡ አስታውሳ!
ሞት'ኮ፡ ዕዳ፡ አለብህ፡ የማታ፡ የማታ።
ይህን፡ ብቻ፡ እወቅ፡ ደግሞም፡ እንዳትረሣ!
ብሎ፡ ጠቀለለ።

ይህ፡ ሕግ፡ ተፈጥሮ — የምሩን፡ አምርሮ፤
ድንገት፡ ዱራሽ፡ መርዶ፡ ቢሆንበትና፤
ሀሩን፡ አልራሺድ፡ ካንገቱ፡ አቀርቅሮ፡ ከሆዱ፡ እንደባባ፤
ከመጽሐፉ፡ ገፅ፤ ከሚያነበው፡ ክፍል፡
ድንገት፡ ጠብ፡ አረገ፡ እንዲት፡ ዘለላ፡ እንባ።

ሄንሪ፡ ሎንግፌሎ፡ 'ሀሩን፡ አልራሺድ'፡ በሚል
ርእስ፡ ከፃፈው፡ ተካቶ፡ የተተረጎመ።
ግንቦት፤ ፲፱፻፷፩ ዓ.ም.

## እየጠሩ፡ማባረር

አንድ፡ቀን፡ቅዳሜ፡ጠብሸ፡ወገረኝና፣
በእግሬ፡ልንሸራሸር፡ፒያሳ፡ወጣሁና፣
ዐይኔ፡ሲቀላውጥ፣ ልቤም፡ሲለው፡በርታ፣
ዐይኔ፡ቅልውጡን፡አቁሞ፡ላንዳፍታ፣
ሂዱ፡ትክል፡አለ — ካንዲቱ፡ኮረዳ፤
ሚጢጢ፡ነገር፤
ባላፍሮ፡ጠጉር።

ሚጢጢዋ፡ነገር፣ፍርጥምጥም፡ብላ፣
በቅኝ፡ዐይኗ፡ኮርነር፡እንዴ፡ገረፈችኝ፤
ስማይል፡አጠጣችኝ።
ስማይሏ፡ደግሞ፡ካተያይዋ፡ጋራ፡በሳል፡በመሆኑ፣
እንዲህ፡ያል፡ብስለቱ፣ ሚጢጢ፡ገላዋን፡አለመመጠኑ፤
ቆህ፡አንድ፡ላይ፡ሆኖ፡ደግሞም፡ምኑ፡ምኑ፣
ሚጢጢዋ፡ነገር፡እንዴ፡ስትደቃ፣
ዐይኔ፡እንቀላፋና፡ልቤ፡ድንገት፡ነቃ።

ቁሜ፡አየኋት፤
ከመንገዱ፡ባሻገር፣ ካንዲት፡ትንሽ፡መደብር፡
ስትገባ።
ሚጢጢ፡ነገር፣ ገለባ፡የምታክል።
ጠበቅኋት፤ እስክትወጣ — ደሞ፡ላያት፣ ደሞ፡ልመኛት።

ብቻ — ሚጢጢዋ፡ ስትወጣ፣
ከጎኗ — አንድ፡ ት — ልቅ፡ አፍሮ፣
ኃይለ — ኛ፡ የመሰለ፣ ግንባሩን፡ ኮስትሮ፣
ራ — መድ፣ ራ — መድ፡ ሲል፡ አይቼ፣
እኔ፡ ሆየ፣ እ — ጅጉን፡ ፈርቼ — ፈርቼ፣
ራሴንም — በጣ — ም፡ ታዝቤው፡ ታዝቤው፣ ታዝቤው፣
አፍሮንም፡ ስድቤው፣ ስድቤው፣ ሰ — ድቤው፣
(በሆዬ)

ጠብሼን፡ አቅፌ፡ ተመለስኳት፣
ወደቅዳሜ፡ ሽርሽር፤
ወይ፡ የሚጢጢ፡ ነገር!
ወይ፡ ጠርቶ፡ ማባረር!
እያልኩ።
በሆዬ።

ኅዳር፡ ፯፣ ፲፱፻፷፭ ዓ.ም.

## ኧረ፡ በፈጠረሽ!

ንግግር፡ አብቅቼ፡ አፌን፡ ተለጉሜ፤
ንግግር፡ አብቅተሽ፡ አልናገር፡ ብለሽ፤
ስለተኮራረፍን፤
ፀሀይ፡ ተሰበረች፣ አላበራም፡ ብላ፣
ጨረቃም፡ ጠፋችው፡ ዱንግጣ፡ ኮብልላ፣
ዳግም፡ ጻቦ፡ ላትጥል፡ ተፈጥሟ፡ ምላ!
እኔና፡ አንቺ፡ ብቻ፡ አለነው፡ ከዚሁ፣
ከኰርፈሽ፣ አኰርፌ፣
ኰርፍርፍ፡ ብለን፣
ፍጥረት፡ እስኪደንቀው፡ የእኛ፡ እንደዚህ፡ መሆን።
ኧረ፡ በፈጠረሽ!
አንዴ፡ ሣቅ፡ በይና፡
ፀሐይ፡ ብልጭ፡ ትበል፣ ህይወት፡ ትሥረፅና።

፲፱፻፷፫ ዓ.ም.



## የዋህ፡ፍቅር

ሰማይና፡ምድር፡
ሁለቱ፡ተጋብተው፣
ሙሽራ፡ቤት፡ገብተው፤
ፀሀይ፡አቀኝቅና፣
ተገልሮ፡ደመና፣
ሁሉም፡ሲዪሰቱ፡
ተፈጥሮን፡ረስተው፣
በሀሴት፡ረክተው፤
ድንገት፡ሠቅቅ፡አሉ፡፡
ሁሉም፡ተቃለሉ፡፡
ፀሀይቱ፡አብቅታ፣አቁማ፡ቅኝቀና፣
የመሬት፡የሰማይ፡— ሀሴታቸው፡በቃ፡ጋርዷቸው፡ዱመና፡፡
ታዲያ— ለዚህ፡ዓይነት፡ፍቅር፡
ሁሉም፡ሁኖ፡እንግዳ፣
ልዩ፡ናፍቆት፡ነግሦ፣
ምድር፡ሲቃ፡ቢ'ሻት፣
ሰማይ፡አለቀሰ፡እሷን፡ተንተርሶ፡፡
ለዚህ፡የዋህ፡ፍቅር፡፡

፩፱፻፲ ዓ.ም.



## ቡና?... ማኪያቶ?

ምክኑስ? አልኩ።
ነገሩ፡የምፀት፡ነው።
ብዙ፡አስቤ፡ተመራምሬ፣
በለቀምኩት፡የዕውቀት፡ጥሬ፣
በዚህ—የኑ-ዐዋቂነት፡ኢተኩሬ፣
ራሴን፡ከፍ፡አድርጌ፣ አክብሬ፣
በለቀምኩት—ባካበትኩት፡ጥሬ፡ዕውቀት፡ብዙ፡ኮርቼ፣
ከኩራቴም፡ብዛት፡
ብ-ዙ፣ አጅጉን፡ብ—ዙ፡ታብቼ፣ አ—ጅጉን፡ብዙ፡ቆይቼ፣
ድንገት—እንደው፡ድንገት፡
ጎዶሎ፡አንደበቴ፡ብትፈታ፣ አንዲት፡ጥያቄ፡ተጠይቄ፤
'ቡና፡ይምጣልህ፡ማኪያቶ?'
የምትል፤
'ለማንኛውም፣ እስቲ፡ጉዳዩ፡ይቅረብልኝ
'በመጀመሪያ፡ተጠንቶ'
ብየ፡ተናገርኩኝ፤
ጥናት፡ልምድ፡ሆኖብኝ።

ሊጠጣ፡የቀረበ፡ቡና፡—እናም፡ማኪያቶ፣
እንዲመለስ፡ሆነ፣ሊቀርብ፡ተጠንቶ።

ሲጠና፣

ሁሉም፡በረዶና፤
በሪዱ፡ቆይቶ፡ቀረበና፤
በመብረዱ፡ተናቀና፤
ሊጠና፡የሄደው፡ማኪያቶ፣ ደግሞም፡ቡና፣
ተጎልቶ፡በዚያው፡ቀረ፤እንዳልነበረ፡ተረሣና።
ደግሞ፡እስኪፈላ፡ሌላ፡ቡና።

መጋቢት፣ ፲፱፻፷፯ ዓ.ም.



# ዕፀ፡በለስ

በለሴ፡ሁነሽ፣
ልምላሜሽ፡የስሜት፡ልቤን፡የሚመታ፣
አንዴ፡ብቻ፡ገምጬሽ፡በፍርሃት፡ሳላመነታ፣
እርቃንነቴን፡ባወቅሁት።
ደመ፡ነፍስ፡ህይወት፡ባላልገየኝ፡ባስነሣሁት፣ባነቃሁት።
ከዚያም፡ብሰዱድ፡ባልከፋኝ፡—
አለሁበት፡ለሚባል፡ገነት፡ባይተዋር፡ሆኜ፤
ሰውነቴን፡አውቄ፣አዳምነቴን፡አስተንትኜ።
ዕፁብ፡ሚጠትን፡እንዳደርግ፡ወዳንቺ፡
ዕፁብ፡ተራክቦን፡ካንቺ፡ጋራ፣
ለስሜቴ፡በለስ፡ሁኚኝ፤ አትጠውልጊ፡አደራ።
በለሴ— በለሴ!
እንዳልሆን፡የስሜት፡ብቻ፡ቊራኛ፣
እንዳልሆን፡የስሜት፡ብቻ፡ብቸኛ፣
አሁንም፡ደግመሽ፡ለምልሚ፡እልፍ፡ሺ፡ዘመን፡እንዳልተኛ።
ራቁቴን፡መሆኔን፡አብስሪኝ፡ብትመሪም፡ቅሉ፡ባውቀው፣
ስሜቴ፡ብቻ፡ተንሠራፍቶ፡የሰው፡አእምሮየን፡እንዳይጨንቀው

መጋቢት፣ ፲፱፻፷፯ ዓ.ም.



## ምኞት፡ፈረስ፡ቢሆን...

...ዓለሙን፡ጠፍጥፌው፡ቂጣ፡በጋገርሁት፣
ውሀውንም፡ንጬ፡ቅቤ፡ባወጣሁት።
ባወጣሁት፡ቅቤ፡ቂጣየን፡አርሼ፣
ጨጨብሳ፡ጭብጦ፡አድርጌ፡ለውሼ፣
አንዴ፡በገመጥሁት—አንጀቴን፡ባራስሁት።
የዋጥሁትን፡ውጬ፡የሰለቀጥኩትን፣
ከዚያ፡'ሚተርፈኝን፡—
ምኞት፡ኃይል፡ቢሆን—
ያድበለበልኩትን፡ጨጨብሳ፡ጭብጦ፣
ትንፋሽ፡ለቅቄበት፣ከእጄ፡ነፃ፡አድርጌ፣
አጉልቼ —— አሳድጌ፣
ዓለሙን፡በተውኩት፡በመሬትነቱ፣
ዳግመኛ፡እስክመኘው፣ሊሆን፡እንደጥንቱ።
ብቻ—ምኞት፡ፈረስ፡ሁኖ፡አይጋልብም፡ሜዳ፡የሽምጥ፡አይሄድም
ዶንገላሣ፡አይመታም፤ሶምሶማም፡አይረግጥም።
እና፡የኔም፡ውሀ፡ቅቤ፡ሁኖ፡ቀልጦ፡ጭብጦ፡አያሠራም፤
የሚሾረው፡ዓለም፡ምኞቴን፡አይፈራም።
ገላምጦኝ፡ያልፋል፣ሳይፈታ፡ሬቱ፣
በሕግ፡ተፈጥሮው፡በታሪክ፡ሥራቱ፣
ዓለም፡እንደወትሮው፡ዓለም፡እንደጥንቱ።

መጋቢት፣ ፲፱፻፷፯ ዓ.ም.

## ምፀት

ሁላችንም፡ነን፡
ወንድማማቾች፤
እንደቃየል፣ እንደአቤል፤
እንደሁለቱ፡ የአዳም፡ ልጆች።

ከጆን፡ፖከር፡ግጥም፡የተተረጎመ
፲፱፻፷፫ ዓ.ም.

## አታድርስ!

መዝጊያዋን፡ቆርቍሮ
ድምፁን፡ባታሰማ፣
ሽቶና፡ጠይቆ፡ቀኗጅ፡ብታቅማማ፣
በሌሊቱ፡ግርማ።
በጠራራ፡ፀሀይ፡ካደባባይ፡ወጥቶ፣
ድምፁን፡ከድምፅ፡ይልቅ፡ሺህ፡ጊዜ፡አጣፍቶ፤
'ቆዳየም፡ይገፈፍ፡ይሁንልሽ፡ጫማ፡
'እኔ፡ምን፡ቸገረኝ፡ላንቺ፡ከተስማማ'
ብሎ፡አንቆረቆረ፡
የጊዜውን፡ዘፈን፣ የዘመኑን፡ዜማ።

## ጊዜን፡ተፍቼበት

ጊዜን፡ንቄው፣ በጎን፡ተመልክቼ፣
ምላሴን፡አውጥቼ፣ ምራቄን፡ተፍቼ፣
እንዳይሸጥ፡እንዳይለወጥ፡አድርጌ፣
ስድብ፡አውርጄበት፣ ሣቻን፡ጨምሬበት፤
ይህን፡ ሁሉ፡አድርጌው፤
‘ስድብ፡አይለጠፍ!
‘ታዲያ፡ምን፡አለበት!’
ብሎ፡ካለኝ፡ኋላ፤
ቀና፡ብሎ፡ሊያይ፡ቃል፡ገባልኝና፡
አይሥቁ፡ሣቅ፡ሥቆ፣ ዝም፡ብሎኝ፡አለፈ፣
ከቶ፡ምን፡ቸግሮት፤ ምን፡ደንታ፡አለውና!
ከቆምኩበት፡ትቶኝ።

በቀደምለት፣ ፲፱፻፷፫ ዓ.ም.

ራእየ፡ግምበኛ፡ዘአራዳ፡ጊዮርጊስ

ህይወት፡ የወጠነለት፤ ወይስ፡ የወሰነበት፤
የዐርባ፡ ቀን፡ ዕድሉ፡ የጫነበት፡ አክሊል፡ ይሆን?
በተለይ፡ ግዘፉ፡ ረቆ፤ መንፈሱ፡ ግዘፍን፡ ነሥቶ
ግዘፍን፡ ነዋቆ፡ ይሆን
የህልውናው፡ ዘፀቤ፡ ይከሰትለት፡ ዘንድ፡ ያበቃው?
　　　　ወይስ
　　　　'ኅሩያን፡ በህልውናሆሙ፡ ጻድቃን፡
　　　　　　　　በሕ'ገጋቲሆሙ
　　　　'ልዕሉዕ፡ ከመ፡ መዳልው፡ በፍትሆሙ'
ተሰኘተው፤— በመላእክት፡ ቋንቋ፤
ከእንጨት፡ መርሮ፡ ለታቦት፤ ከሰው፡ መርጦ፡ ለሹመት፡
እንዲሉ
　　　　'ዘኅረዩ፡ አርእስቲሆሙ'
እኔህ፡ የመፀወቱት፡ ትሩፋት፡ ጊድራት፡ ይሆን፡
ለማኅበረ፡ ሰብ፡ ባይተዋር፡ መሆንን፡ ሹክ፡ የሚልለት?
እውነታውስ— እሱም፡
　　　　ለባዊ፡ መሆኑ፤
　　　　ነባቢ፡ መሆኑ፤
　　　　ገባሪ፡ መሆኑ።
ብቻ፡ የማይገባው፡
ሕግ፡ ኅሩያን፡ የሱን፡ ሰውነት፡ ሲለካ፡
ሰብእናው፡ የተገላቢጦሽ፡ በኅዳጣኑ፡ ጠገግ፡ ሲጠለል፡—

ይኼ፡ነው፡የማይገባው።

ቋንቋው፡የመላእክት፡ሁኖበት።

ምሥጢሩ፣

ጥበበ፡ነገሩ፣

'የመለኮት፡ባህርይ'፡ምሥጢሩ።

ባንድ፡ጠገግ፡ጭንቅት፡—

ስለት፡ሲያብጥ፣

ጥማት፡ሲያንቅ፣

ግራ፡እየገባው።

ባንድ፡ጠገግ፡ጥበት፡—

ሰው፡ማስቸገሩ፡

ሲያጣ፡ማፈሩ።

ሁለቱም፡አንድ፡ናቸው፡ለነገሩ።

ብቻ፡ሁሉም፣ ሰብእናውን፡እየወጋው፡—

ትንሽም፡ቢሉ፡ጠቅታ— መከፋቱ።

ባንድ፡በኩል፡ተስፋ፤ ደግሞ፡ነገ፡ምኞቱ።

መከፋቱ — ተስፋው — ምኞቱ (ተው፡ቻለው፡ሆዬ፡ደለኝን?

ማጣቱ፣

ምሬቱ፣

ቁጣው — ንዴቱ —

እብዴቱ — እብደቱ — እብደቱ!

እንጃ! ሌላው፡ዘፋኝ፡ልክ፡ብሏል፤

ከልክ፡በላይ፡የታመቀው፡ይፈነዳል።

ወይ፡ይገድላል

ወይም፡ደግሞ—አይግረመንና—ይሞታል።

ጥር፣ ፲፱፻፷፮ ዓ.ም.

# ጨረቃ

፩

ጨረቃ፣ ድንቡል፡ቦቃ፣
ጊዜ፡ባለዕጣ፡አድርጓት፡በፈረቃ፣
ከአጼ፡ቤት፡ቁልፊት፡ተላቃ፣
ድቅድቅ፡ጨለማን፡ገፋ፣ ጠረር፡ሸንተረሩን፡አጥለቅልቃ፣
ትመራው፡ያዘች፡ተጋዳዩን፡
ታሳየው፡ወጣች፡የሰበሩ፡ሰካ፡ጎዳናውን።
ጨረቃ፡ድንቡል፡ቦቃ፣
ከአጼ፡ቤት፡ነጥቃ፡ለቃ፣
ከተጋዳዩ፡ሰፊ፡ሜዳ፣ ከጠረር፡በላይ፡ደምቃ፡—
ከጠረር፡ያሉ፡ተጋዳዮች፡
ተኮሱ፡ተኳኰሱ፤
ጠላትን፡ደመሰሱ፤
ደረቅ፡ቂጣ፡ሬፋ፡ቆሎ፣
አዬን፡ትተሽ፡ከኛ፡ቶሎ፤ — ብለው፡ያወደሷት፣
በፀሀይ፡ቦታ፡ቅርሴ፡ብለው፣ በሌት፡ባድማ፡የጠቀሷት፤
ፍቅረኞች፡የብቻ፡ብለው፣ ማር፡ጥፍጥናዋን፡ሲቀምሱ፣
ታጋይም፡ደግሞ፡የብጤቱን፣ ትጥቁን፡አድርጎ፡ትራሱ፣
ያወድሳታል፡በግብሯ፡
ያዜምላታል፡በውጤቱ፣
ጨረቃ፡ውቢቱ፣ ፀሀይ፡የሌሊቱ።
ህልውናዋ፡የነበረ፡በግቢ፡ቁልፊት፡ተወስኖ፣

አዳር፡ጉዞዋ፡የዘመኑ፡ከተጋዳዩ፡ጣምራ፡ሆኖ፣
ተመራው፡ያዘች፣
ፋና፡ሁና፡በሌት፡— አቅፋ፡ደግፋ — ዱካውን፡እያሳየች።

፪

ጨረቃ፡ድንግል፡ቦቃ፡
ህፍረት፡ሁኖባት፡መጋለጡ፡በደመና፡ጂርባ፡ተደብቃ፣
ደብዛዝ፡ባለ፡ፈገግታ፣ በለሆሳስ፡ፍቅር፣
የታጋይ፡እርምጃውን፡ስትማትር፣
ስትስብ —— ስ-ታስ-ጠ—ጋው፣
ድንገት፡ጬኸት፡በረከተ፤
ታጋይ፡ተኩሱን፡ከፈተ፣
የጠላትን፡ኼላ፡አነካከተ፤
ጨረቃ፡ፍቅሩን፡ተመለከተ።
ጨረቃም፡ድንግል፡ቦቃ፣
ህፍረት፡ሁኖባት፡መጋለጡ፡ሌት፡የነበረች፡ተደብቃ፣
ዕርቃን፡ብርሃኗን፡ወረወረች፤
ከደመና፡ግርዶሽ፡ወጥታ፡ተፍለቀለቀች፣
ዐይኗ፡ጥላዋ፡ተገፎ፡ዕርቃኗ፡ምድሩን፡አለበሰች።
ሜዳ፡ሸንተረር፡ተኳኩሎ፡ከጨረቃ፡ጋር፡ተጣቀሰ፤
ታጋይ፡ውበቷን፡አወደሰ — መጋለጧንም፡ቀደሰ።
በዚች፡ዕርቃን፡ብርሃን፣ ከዚች፡ዕርቃን፡ብርሃን፣
ከታጋይ፡ተራክቦ፡
ድል፡ተወለደና፡የሰው፡ልጅ፡ታወቀ።
ታጋይ፡ፈነደቀ! ታጋይ፡ፈነደቀ!

፲፱፻፷፩/፷፪ ዓ.ም.

## አዲስ፡ግጥም

እግዜር፡ትእዛዙ፡ተሽሮ፣ ቃል፡ቃልነቱ፡ባይከበር፣
አንዲት፡ፍሬ፡ተበጥሳ፣
አንዲት፡ፍሬ፡ተቀምሳ፤— የገነት፡መውጫው፡ቢሰበር፣
በዚህ፡ተቆጥቶ፣
‘አዳም፡አባተ፡ሔዋንም፡ደግሞ!’
ብሎ፡ተጣርቶ፣
‘ያላቆጠ፡ያድበለበላችሁ፡
‘እጄ፡ሳያጠፋችሁ፣
‘ውጡልኝ፡ከዚህ! ውጡልኝ፡ብቻ!
‘ከዚህ፡ያቆማል፡የትዕግሥቴ፡ዳርቻ!’
አለና፣
አዳምን፡(ከነሚስቱ)‘ብላዕ፡በህፈ፡ገጽክ!’
ብሎ፡ሲረግመው፣
አዳምነቱን፡ቀደሰ፤
በዚህም፡የገነት፡ኪዳን፡ፈረሰ፡
የገነት፡ድንበር፡ተጣሰ።
ቁልቁል፡ውረድ፡ሲለው፡ ወደምድሩ፣
አዳም፡ከነሚስቱ፡በእዱ፡ጥበብ፡ሙያ፡ከበሩ።
ተልዐሉ፤ ዐረጉ፤
ተቆራኛቸው፡ቅዱስ፡ሰይጣን፡ሠርቶ፡የመፍጠር፡ማዕርግ!

አዳም፡ከፈጣሪው፡ቢጣላ፣
የፈጣሪነት፡ክሂሎቱ፡በተረገመው፡ቤቱ፡ሲሞላ፣
ቃል፡ግዘፍን፡ነሣ፤
ነፍስ፡አካልን፡ገዛ፤
አዳም፡ትስብእት፡ቆመ፡በእዱ፡ጥበቡ፡በዛ።
ዳንጊያን፡ከዳንጊያ፡አማርጦ፣ ዳንጊያን፡ከዳንጊያ፡አፋጭቶ፣
ብዙ፡ፈጠረ፤ ብዙ፡አመረተ፤
በመፍጠሩ፡የሰውነት፡ውበቱ፡ተከሰተ።
በወዝህ፡ብላ፡ተብሎ፡መረገሙ፡ቡራኬ፡ሁኖ፡ተገኘ፤
የሰውነቱን፡ልዕልና፡በተፈጥሮ፡ውስጥ፡እየናኘ።
ዳንጊያን፡ከዳንጊያ፡አዋቅሮ፣ ዳንጊያን፡ከዳንጊያ፡አማርጦ፣
በእዱ፡ጥበቡ፡አስጊጦ፤
ቃልን፡በዳንጊያ፡ግዘፍ፡ኃይል፡ግዘፍ፡አሲዞ፡አግዞ፣
ከምድር፡ቢያወርዱው፡ጊዜና፣
ቃሉ፡ፍፃሜን፡አገኘ፡አዳም፡የሰው፡ልጅ፡ሆነና።
ቃል፡ቍልቍል፡ወረዱ፤
ፍፁምነቱ፡በዳንጊያ፡ግዘፍ፡ታገዱ፤
በወላድ፡ምድር፡ማኅፀን፡የኪነት፡እሳት፡ነደደ።
አዳም፡ወልዱ፣ በሥቃይ፡በሲቃ፣
ቃልን፡ጨበጠና፣ ሥጋ፡አለበሰና፤
ተፈጥሮን፡አድንቆ፣ ተፈጥሮን፡መልምሎ፣ ተፈጥሮን፡አርቆ፣
በእዱ፡ጥበብ፡ሙያው፡ራሱን፡መርቆ፣
ዳግም፡በፈረቃ፡
አዳም፡ቀንጆን፡ወልዱ፡ለአብነቱ፡በቃ።

፲፱፻፸፪ ዓ.ም.

## የመኖር፡ምፀቱ

አሁን፡-እዚህ።
አሁን— በዚች፡ደቂቃ፤
በምጥ፡የተያዘች፡እናት፡በታላቅ፡ሕማም፡ተጨንቃ።
ጭንቅም፡ቢሉ፡ግና፡በዚች፡ደቂቃ፡
ይችው፡ወላድ፡በህይወት፡ጀርባ፡ተደብቃ፣
ስታቃሥት፡-በሥቃይ-በሲቃ
አንዲቷ፡ደቂቃ፡አለፈች።
ጊዜም፡በዚያው፡ልክ፡ተራምዶ፡ደግሞ፡በዚያው፡ልክ፡አጠረ፤
አንድ፡የሕይወት፡አምሳል፡ዐይኑን፡ወደዚች፡ዓለም፡ማተረ፤
ህፃን፡ተወለደ።
ግና፡ደግሞ፣ በዚያች፡አፍታ፡የአንዲት፡እናት፡ህይወት፡ታገደ።
ባንዲት፡አፍታ!
አንዲት፡ደቂቃ፡ስታልፍ፡ሌላ፡ደቂቃ፡ተተክታ!
በዚህ፡ዕፁብ፡ሂደት፡— በዚህ፡የእድገት፡ምሥጢር፣
ከዕቃ፡ወደዕቃ፡እንደሚገላበጥ፡ነገር
ስትፈሥ፡ስትሞላ፡የሰው፡ህይወት፣
በዚህ፡ዕፁብ፡ትንግርት፡በዚህ፡ዕፁብ፡ሥራ፡
ህይወት፡አንድ፡አምባ፡ለቃ፡ሌላ፡ማኅደር፡ስትሠራ፣
ዕፁብ፡እንጂ፣ የሚያስደምም፡ዕፁብ፡ሥራ።
እነሆም፡ዳግም፡በዚህ፡አፍታ፡
በዋይታና፡በዕልልታ፣
ልብ፡ተሰንጥቆ፡ሲያመነታ፣

ከዚህ፡ግዑዝ፡ብዕር፣ካንዲት፡የቀለም፡ጠብታ፣
የመኖርና፡ያለመኖር፡መራር፡ቅኔ፡ከነምፀቱ፡ተፈታ፡፡
አንድ፡ህፃን፡ሲወለድ፡—አንዲት፡እናት፡ሙታ።

፲፱፻፷፱ ዓ.ም.

## ክብሪት

አንድ፡ተሸ—ሽታ—ጣ-ጣ-ጣ-ታ፣
የሥቃይ፡ድምፅ፡—የቃጠሎ፣
አንድ፡ሹክታ—በለሆሳስ— እሮ—ዬታ፣
ከዚያ፡ዱግሞ፡ከባድ፡ዝምታ፡፡
አንዲት፡ክብሪት፡ስትሞት፣ነዷ፡ተቃጥላ፣
ዕጣዋ፡እንጂ፡ነው፡ተባለና፡
እንደማንኛውም፡ነዳጅ፡እንደሌላ፡ክብሪት፡ሁላ፡፡
ሥቃይ
ሲቃ
እሮዬታ
ዝምታ
ክብሪት፡ነዷ፣ ክብሪት፡ሞታ፡፡

፲፱፻፷፩ ዓ.ም.

# የስሜት፡ንፃሬዎች

## ፩

ዛሬን፡በመንገድ፡ላይ፡ስዳክር፡ቆይቼ፣
አላፊ፡አግዳሚውን፡
አፋሽ፡አጎንባሹን፡
በፊርጁ፡ለይቼ፤
ሳበጥረው፡ውየ፡መሸ፡ሳበጥረው፣
ስንዴና፡እንክርዳዱን፡ጨርሼ፡ሳልለየው።
ሁሉም፡ተዛነቀ፤
በመለየት፡ሲቃ፡በእንባ፡ተናነቀ።
ራሱን፡አቀፈ፣ሳመው፡አገላብጦ፤
አይዞህ፡ባዩን፡ቢያጣ፡ጊዜው፡ተለውጦ።
(እጉል፡ጊዜ፡ብሎ)
እጉል፡ጊዜ፡እንበል፡ጊዜ፡ምን፡አጠፋ፡
ቢያቀኑት፡ሊቀና፡ቢደፉት፡ሊደፋ።
አቅኚ፡አዘናባዩ፣
ህይወት፡ሰጭ፡ገዳዩ፣
የኛው፡እንቅስቃሴ፡ብቻ፡እንጂ፡ነውና፣
ብዙ፡ምች፡አይምታን፤ እንየው፡በጥሞና፤
አንጋለጥ፡ብዙ።

ስሜት፡ራዱ፤
ወኔ፡በረዱ፤
ኅሊና፡አደገደገ

ሂዴት፡ማለገ።
እንበስል፡ሲሉ፡ፀሀዩ፡ገሮ፣
የተጣደው፡እሮ፣
አብሽሎ፡እንኳ፡አልሆነም፡መረረ፤
ወገን፡ከወገኑም፡አልተቋጠረ፤
ወኔ፡ታነቀ፤
አእምሮ፡ከስሜት፡በእንባ፡ታዛነቀ፤
አለቀ፡አሉና፡ዱቀቀ።
አሁን፡ተምን፡ጊዜው፡ማተቡ፡ወለቀ።

፪

እሳትስ፡ነድዶ፡ነበር።
የተስፋ፡ምላሱ፡የነፍስን፡ጠሊቅ፡ማኅደር፡እያሞቀ፣
በፍሥሐ፡ወሀሴት፡ፅርሐ፡አርያሙን፡ሊዳስ፡እየነጠቀ፣
ህያውነቱን፡ሊያፀድቅ፣
እመቀ፡እመቃቱን፡ሊለቅ።
ሊበር፣ሊወረወር፣
ከኮከብ፡ጋር፡ሊሰምር፤
ዓለሙ፡ዓለማቱን፡ሊሞላ፣
በረድን፡አቅልጦ፡ሊዴላ፣
ህልም፡መሆኑን፡ሳያውቅ።
የሰው፡ልቤ፡እንዲህ፡እያለ፡ሲያስላ፣
እሳት፡ቀብጦ፡
በረድን፡አቅልጦ፣
ባንዲት፡የውሃ፡ጠብታ፣

ኣለሁ፡ ይል፡ የነበር፡ የነፍስ፡ እቶን፡ እሳት፡
በበረድ፡ ተፈታ።
እናም፡ በፈረቃ፤
እናም፡ በፈረቃ፤
እሳት፡ በረድ፡ ሆኖ፡ በረድ፡ አቃጠለ፤
ባያል፡ ቅዝቃዜ፡ ነፍስ፡ ተቃጠለ፤
ኩምትር፡ ኩምትር፡ አለ።
እሳት፡ ተሸነፈ፤
በሞቀው፡ ነፍሴ፡ ውስጥ፡
አንድ፡ ትልቅ፡ በረዶ፡ ገብቶ፡ ተወተፈ።
እውነቱን፡ ለፈፈ።
ነፍስ፡ መታመሙን፡ በቆፈን፡ ተይዞ፡
በምናብ፡ እውነታ፡ ታሥሮና፡ ተግዞ።

፫

በመጀመሪያ፡ ፍቅር፡ ነበረ።
ፍቅርም፡ የሰው፡ ሆነ።
ፍቅር፡ አካል፡ ሲገዛ፤
ነፍስ፡ አግብቶ፡ ሲተነፍስ፤
ሙቀቱ፡ ህይወትን፡ ዘራ፤
የስሜትን፡ ፋና፡ አበራ።
በዚህ፡ ጮራ፡
በሰውነት፡ አምባ፤ በሰውነት፡ ጎራ፡
ወበራ፡ ተደግሶ፤
ካዓድ፡ ማድጋ፡ ፉት፡ ተብሎ፤ ካንድ፡ መሠሪያ፡ ተቆርሶ፤

ባንድ፡በልቶ፡ጠጥቶ፣
ባንድ፡አውርቶ፤
ደስታን፣ተስፋን፣
ድካም፡ብርታቱን፡ተጨዋውቶ፣
ተስማምቶ፡ተግባብቶ፣
ልብ፡ለልብ፡ተጎራብቶ፣
ባንድ፡ምጣኔ፣ባንድ፡ዜማ፣
ሁለት፡የተለያየ፡ነፍስ፡ቃል፡አልባ፡ሲስማማ፣
አንዱ፡በሌላው፡ሁኖ፤
አንድነት፡ይፀድቃል፤ፍቅር፡ደግሞ፡ይሠርቃል፤
ነፍስ፡ዘርቶ፡ያፈካል።
ትስብእት፡ሊሰግድለት፣
ሐውልት፡ሊቀርፅለት፣
በአምሳሉ።

፬

መናኽሪያውን፡ሥቶ፡ዛሬ፡የባከነ፡ስሜቴ፣
ጭጋግ፡ደመና፡ሸፍኖት፡ማለም፡ያቃተው፡አስተያየቴ፡
አልጠራ—አልሰማ፤
አላረካ፤አላመረቃ።
በዱመ፡ነፍስ፡ጉዞ፡ባገኘበት፡ቃርሞ፡ሊያበቃ፤
ቢጠግብ፡ሊጋደም፡ቢራብ፡ሊያዛጋ።
ጥርስ፡አልነጭ፡ብሎ፡ማኘክ፡ተስኖት፡መንጋጋ፤
ቀን፡በመሸ፡ሌት፡በነጋ፡
አንድ፡ምዕራፍ፡በዘፈቀደ፡ተከፍቶ፡በዘፈቀደ፡ሲዘጋ።

ውሉ፡የጠፋበት — መልህቁን፡ያልጣለ፡መርከበኛ፣
አይንቀሳቀስ፡ዝግ፡ሆኖበት፣
ማዕበል፡አይሎበት፡አይተኛ፤
ግራ፡የመጋባት፡መጋኛ፡እያጮለው።
አላልቅ፡የሚል፡ተስፋ፡ዲግሞ፡እያማለለው።
ተጠምዶ፡ተጋርዶ፤
ታሥሮ፡ተቆንድዶ፤
ጋይቶም፡ይሁን፡ነዶ፤
ጠልቶም፡ይሁን፡ወዶ፣
ዛሬን፡ለነገ፡ያማሣል፤
ዐመድ፡ሊለብስ፡ይወዛል።
ምን፡ስም፡ይውጣ — የክርስትናም፡ይሁን፡የዳቦ፡
መለዮ፡ጠፍቶለት፡እንኪያስ፡ኪቀር፡አልቦ።
እስቲ፡ስም፡አውጡለት፡ለዚህ፡ለክስተቱ፤
አልሆንልኝ፡ቢለኝ፡እኔ፡ባለቤቱ።



## ትንሽ፡ኮከብ

ስትርቅ፡እየጎላች፣ ስትቀርብ፡እያነሰች፣
ለትርጉም፡ላንድምታ፡ፈጽሞ፡ያስቸገረች፣
አንዲት፡ትንሽ፡ኮከብ፡ውብ፡ብርሃን፡ነበረች።

ከሩቅ፡ስትጠቅሰኝ፡
እተኩሬ፡ሳያት—
ሳያት፡ስማትራት፤
እልፍ፡አእላፍ፡ጨረሮቿ፣ የብርሃን፡ጣቶቿ፡ሲዳስሱኝ፣
የሠራ፡አካላቴን፡ሲዳብሱኝ—በዝምታ።
በልቅረብ፡አልቅረብ፡መንታ፡መንገድ፡ተሰንጥቄ፡ሳመነታ፣
ጠበቅ፡አድርገው፡እንዲይዙኝ፡ስመኛቸው፣
ወትሮ፡ሲያማልለኝ፡የሩቅ፡ዝምታ፡ሙቀታቸው፣
እልፍ፡አእላፍ፡ጨረሮቿ፣
እኒያ፡የረቂቅ፡ብርሃን፡ጣቶቿ፣
ያንዲት፡ትንሽ፡ኮከብ።
ይህችን፡ሩቅ፡ፈለገ፡ብርሃን፡ቀርቦ፡የማየት፡ፍላጎቴ፣
ፈተናዬ፡እጅግ፡በዝቶ፣
በምሕዋሯ፡ተጠምዶ፣ ግን፡በርቀቷ፡ታግዶ፤
እንድም፣
ለብ፡ባለ፡ሙቀቷ፡ሊታጠብ፡ሲሻ፡ህይወቴ፣
የማላውቀውን፡ቃጠሎዋን፡ደግሞ፡ወትሮ፡ሲፈራ፡ሰውነቴ—
ሥጋ፡ሥሡነቴ፤

አንዲት፡ ትንሽ፡ ኮከብ።
ምኞቴ — ለብ፡ ባለ፡ ሙቀቷ፡ ህይወቴ፡ ሊታጠብ፡ ሲሻ፣
ፍርሃቴ — ከእልፍ፡ አእላፍ፡ የ'ሳት፡ ላንቃዋ፡ ሥጋየ፡ ቢያጣ፡ መሸሻ፤
ባሕርይዋ፡ ኅቡእ፡ ሁኖ፡ ዕውቀቴ፡ ጠፍቶት፡ መዳረሻ፤
የሩቅ፡ ማኅቶት፡ ብሕትውናዋን፡ መረዳቱ፣
አልወጣ፡ ብሎኝ፡ መርምሮ፡ የማወቅ፡ አቀበቱ፣
ወድቆ፡ የመነሣት፡ ብላቱ፣
ተቃጥሎ፡ የመብረድ፡ እርካቱ፣

ያንዲት፡ ትንሽ፡ ኮከብ።
በዝምታ፡ ትግል፡ ውስጥ፡ ፈንጠር፡ ብላ፡ መጥቃ፣
የምታበራ፣ ህዋውን፡ ሰንጥቃ፣
የብርሃን፡ ኢጣቢዋን፡ ካድማስ፡ ባሻገር፡ ፈንጥቃ፡
ዓለመ፡ ዓለማቱን፡ ተገን፡ አርጋ፣ ሰሬውን፡ ፅልመት፡ ንቃ፤
ስትርቅ፡ እየጎላች፣ ስትቀርብ፡ እያነሰች፣
ሊትርጉም፡ ላንድምታ፡ ፈጽሞ፡ ያስቸገረች፣
አንዲት፡ ትንሽ፡ ኮከብ፡
ውብ፡ ብርሃን፡ ነበረች።
ብርሃን፡ ሁና፡ ጠልቃ፡ በልቤ፡ ልምሹ፣
አልሠርቅ፡ እያለችኝ፡ ቀናቱ፡ ሲመሹ፣
የምታቀዝዘኝ፣
አንዲት፡ ትንሽ፡ ኮከብ፡
ውብ፡ ብርሃን፡ ነበረች፤
ስትርቅ፡ የምትጎላ፡
ስትቀርብ፡ እያነሰች።
አንዲት፡ ትንሽ፡ ኮከብ።

አንዴ፡ደብዘዝ፣ አሁን፡ቀዝቀዝ፣
አንዴ፡ደመቅ፣ ደማም፡ፈካ፣
ቢርቋት፡ አትጠፋ፣ ቢቀርቧት፡ደማም፡'ማትነካ።
አንዲት፡ብቸኛ፡ኮከብ፣
አንድ፡ብቸኛ፡ልብ፣ ተውጠው፡በዝምታ፣
ቄሱም፡ዝም፡ መጣፉም፡ደማሞ፣
እንዴት፡በዝምታ፡ ሰው፡ይሞታል፡ታሞ።
ባንዲት፡ትንሽ፡ኮከብ።

ያቺ፡ትንሽ፡ ኮከብ፣
ተወርዋሪ፡አይደለች፤
አሳየው፡ ፈለጓን፣ የብርሃን፡ትንግርቷን።
የኅሊና፡ክበብ፣ የአእምሮ፡ጥበቱ፡
ባዕድ፡ለክስተቱ
ታቃጥለኝ፡ታሞቀኝ፡ እንደምን፡ልረዳ፣
ወትሮ፡እየተያየን፡ ዘላለም፡እንግዳ።
መናገር፡ተሥኖት፣ መሞከር፡ተሥኖት፡
የሰው፡ ሰውነቴ፡
ባጉል፡ልማድ፡ፍርሃት፡ሲገደብ፡ስሜቴ፣
ኮከቢቱ፡ደማቅ፡ግዑዝ፡ሆነችና፣
ዝም፡ብላ፡እያየችኝ፡ እልገብቷት፡ሆነና፣
ልቤ፡ቀረ፡መና።
ዝም፡ብዬ፡እያየኋት፣
አንድም፡አልቀረብኳት፤
ወይም፡አልሸሸኋት፤

ባለሁበት፡ሆኜ፡ስማትር፤ ስማትር፤
እንዲሁ፡ላድር፡ነው፡ኮከቧን፡ስቆጥር።
ያቺን፡ትንሽ፡ኮከብ።
ደግሞ፡ትንሽ፡ኮከብ… አንዲት፡ት— ንሽ፡ኮከብ።

ሠረቀ፡ብርሃኗ፤
ጨረር፡ፍንጥቅታዋ፤
የህይወት፡እግቢዋ፤
የማርያም፡መቀነት፡በጭጋጉ፡ግርጃ፤
ሰው፡ምኞ፡ይዞ፡ሊቀርብ፤ ለዚች፡አንዲት፡ኮከብ፤
ለእሷ፡መማለጃ።
እያደነቁ፡ዝም፤
እየተደመሙ፤
ወይ፡ፀንቶ፡እስኪገድል፤
ወይ፡ሽሮ፡እስኪጠፋ፤
የዝምታ፡ሕማሙ።
ያንዲት፡ትንሽ፡ኮከብ።

፲፱፻፸፱ ዓ.ም.



## ጉራማይሌ

እያንዳንዱ፣
ከነፍሱ፡ሌላ— ሌላ፡ነፍስን፡አርግዞ፤
ሁለተኛ፡ገፁን፡ከርእይ፡ማዶ፡አግዞ፤
ሁለት፡ ዐይነት፡ሰውነት፣—
ጉራማይሌ፡ሰው።
አንድ፡ገፁ— የሚታየው— ሲሥቅ፡ሲፍለቀለቅ፣
ሌላው፡ገፁ— ኅቡኡ— ሲታመም፡ሲጨነቅ፤
አንደኛው፣
አንዱ፡ገፁ፣ ደረቱን፡ነፍቶ፣
ሌላው፡ገፁ፣ የተቆለመመ፣
ቅስሙን፡ሰብሮ፣ አንገቱን፡ደፍቶ፤
አንዱ፡ፈክቶ፣ ሌላው፡ከፍቶ፤
ባንድ፡ገፁ፡ ታታሪ፣ በሌላው፡ታካች፡ቦዘንተኛ፣
ባንዱ፡ነቅቶ፡አዳሪ፣ በሌላው፡ሙሉ፡ውሎውን፡የሚኛ፤
ሁለት፡ዐይነት፡ህይወት፡
ሁለት፡ዐይነት፡ሰውነት።
አንዱ፣ አትንኩኝ፡ባይ— ኩርፍተኛ፣
አንዱ፡ሣቂ— ተጫዋች፣ መለኛ፤
አንዱ፣ ሁለመናውን፡ዘግቶ፣
አንዱ፣ ገረገራውን፡ጥሎ፣ ውስጠ፡ውስጡን፡ከፍቶ፤
አንዱ፣ ሠሥትን፡ይቃኛል— በነፈግታ፤
አንዱ፣ ተሳትፎን፡ይናኛል— በእሰይታ፤

ምንነቱ፡

ሁለት፡ዐይነት፡ነው፡ህይወቱ፤
ጉራማይሌ፡ነው፡ሰውነቱ።
አንድ፡ገፁ፡የቆረጠ — ሀሞቱ፡የሆረጠ፤
ሌላው፡ገፁ — ሥጋት፤ ሥጋት፡ብቻ — የሆመጠጠ።
አንዱ፣ ቃናን፡ሽቶ፡ዙሪያውን፡ሲያጣጥም፣
ሌላው፣ ቃናው፡ጠፍቶት — እጁ፡እጁ፡ብሎት፡
ወስፋቱ፡ሲለግም፤
አንዱ — የነፍሱን፡ወይን፣ ሊረካ፡ይጠጣል፤
ሌላው — ምች፡እንዳይመታው — ገፈቱን፡አሽትቶ፡ይሞግል።
ሁለት፡ርእይ፣
ሁለት፡ግብር፤
ጉራማይሌ፡ሰው።
አንዱ፣ ቁጭ፡ብሎ፡ሰማይን፡ይቧጥጣል፤
ሌላው — የቆመበት፡ምድር፡ርቆት፣
እንደላስቲክ፡ይለጠጣል፤
አንዱ፡ያዘግማል፣ ይቆነናል —
ከጊዜ፡ጋር፡ጠብ፡የለውም፤
ሌላው፡ይሮጣል፣ ይባዝናል —
ጊዜ፡ባላንጣውን፡አያምነውም።
ሁለት፡ዐይነት፡ህይወት፣
ባንድ፡ማኅደር — በደባልነት፤
ሁለት፡ገፅታ፤
ጉራማይሌ፡ሰው።



# ስለሚቃጠሉ!

እኔ—
ስለከዋክብቱ፡ምን፡ኣውቃለሁ?
ግን፡ደግሞ፣ በሥነ፡ጥበቡ፡ተመርቄያለሁ፤
በዴግሪ።
እንጂ— እኔ—
ማታ፡ማታ፡
አቤቱ፡መሀረነ!
እንደሚል፡አንጋጥጬ፣ ሰማዩን፡ስመለከት፣
ተገልብጬ፤ ስለማያቸው፡ኮከቦች፡
ምን፡ኣውቃለሁ?
እኔ—
የኒያ፡ስንትስ፡ዝም፡
ቁጥራቸው፡አይታሰበኝም፤
ድምፃቸው፡ አይሰማ፤
መልካቸው፡በውብ፡አይለይ፤
ብርሃናቸው፡የኛ፡ያልሆነ—ረቂቅ፤
ሙቀታቸው፡በእቶን፡ተሠፍሮ፡የማይታወቅ።
ስለኒህ፡ከዋክብት፡ምን፡ኣውቃለሁ?
ግን፡ደግሞ፣ በሥነ፡ጥበቡ፡ተመርቄ፡
ዴግሪየን፡አስመርቄያለሁ።
ስለኒህ፡ከዋክብት፡ቢሉ—
ምንም፡ኣላውቅ፡ግና።

ብርሃናቸው፡ ይስበኛል፤

ቅዝቃዜያቸው፡ የታመቀ፡ ሙቀት፡ ሁኖ፡ አቅፎኛል፤

ዝምታቸው፡ በረጋ፡ አንደበቱ፡ ያጫውተኛል።

ሳይወጡ፡ ሲቆዩ፣ እፈልጋቸዋለሁ፤

ስም፡ ሰጥቼ፣ አንድ፡ ብዬ፡ ለመለየት፡ እመኛቸዋለሁ፤

ባልፈጃቸውም፡ ቅሉ፣

ውዬ፡ አድሬ፡ እቆጥራቸዋለሁ።

እኒህ፡ የሚናፈቁ፡ ከዋክብት፣

ልብ፡ ይሰያሉ።

በተራ፡ ቋንቋ — ዶስ፡ ይላሉ።

ለምን፡ ቢሉ፣

እንዱ፡ የማላውቀው፡ ይኼ፡ ነው — ስለከዋክብቱ።

ግን፣ ዴግሬዬንም፡ አስመርቄያለሁ፤

በቃህ፡ ተብዬ፣

በቃሁ፣ አዎ፡ ብዬ፣ ለመግደርደር፡ በቅቻለሁ።

ታዲያም — እኒህን፡ ከዋክብት፣

እኔ — አውቃችኋለሁ፡ ስል፡ በፈገግታ፣

እረ፡ የለም! አያውቁንም፡ ጌታው!

መልክ፡ አሳስተው፡ ይሆናል! ይላሉ፤

በለዘብታ።

ዐይናቸውን፡ ጭፍን፡ እያደረጉ።

ብዙ፡ ቀን፡ አይቼያቸው፣

አንድም፡ ቀን፡ ኣልለየኋቸውም።

ስለኒህ፡ ከዋክብት፡ ምን፡ ኣውቃለሁ?

ምንስ፡ ብዬ፡ ኣወራለሁ?

ለምን? እንዴት?

ስባልስ?

ላውቅ፡ ብየ፡ እመኛለሁ፤ የዚህንም፡ ጥያቄ፡ መልስ።

ሆኖም፡ ግን፤

ከዋክብቱን፡ አሁንም፡ እቆጥራቸዋለሁ፤

ባልፈጃቸውም፡ ቅሉ።

በየተራ፡ ተለይተው፤ ሳይነጣጠሉ፡

ከዋክብት፡ ተብለው፡ ይታወቁ፡ ዘንድ፡ ብቻ፡

እመኛለሁ።

ባንድ፡ አጠቃሎ፡ ከዋክብትን፡ ማየት፤

የተፈጥሮን፡ ኅፅን፡ ልምላሜና፡ ውበት፡

እንደጥሁም፡ ወይን፡

ቀመስ፡ አድርጎ፡ አጣጥሞ፤

መልካም፡ ሥራ፤

ውብ፡ ወርቅ፡ ዘቦ፤'

ብየ፡ ስለማወድሳቸው፥ ብዙ፡ ያልታወቁ፡ ከዋክብት፡

ምን፡ ኣውቃለሁ?

በህዋው፡ ውስጥ — በገዋው — መልተው፡ ያድጋሉ፤

ዓለመ፡ ዓለማቱን፡ ይሞላሉ፤

በመንፈሳችን፥ ብርሃንን፡ ይፈነጥቃሉ፤ ነፍስን፡ ያበራሉ፤

እጅግ፡ ያበራሉ — ደግሞም፡ ይሞቃሉ፡ — ስለሚቃጠሉ!

ሳይቃጠሉ፡ እንዳይበሩ፡ ግን፡ እሙን፡ ብያለሁ፤

ይህችን፡ ብቻ፡ ተረድቻለሁ — አውቄያለሁ — አምኛለሁ!

ከዚህ፡ እምነት፡ በቀር፡ ምን፡ አውቃለሁ?

ብቻ፡ በሥነ፡ ጥበቡ፥ ተመርቄያለሁ።

ስለከዋክብቱ፡ ግን — ምንም፡ አላውቅ፡ ግና። 

ዋቢያችን

ታሪክ፡ መቼም፡ አይሞትም፣
ከቶ፡ መች፡ ሙቶ፡ ያውቃልና፤
ታሪክ፡ አለፈ፡ ቢባል፣ ባናስተውለው፡ ጊዜና፣
ታሪክ፡ ሞተ'ኮ፡ አያስብልም፤ ታሪክ፡ መች፡ ሞቶ፡ ከቶ፤
ሁሉንም፡ ነገር፡ መዝግቦ፣ ያለውን፡ ሁሉ፡ አኖቶ፣
የዝጌሩን፡ ለዝጌር፡ ትቶ፣ የቄሣሩን፡ በኛ፡ ጥሎታል፤
በኛም፡ የታሪክ፡ ተግባር፡ ታሪክ፡ ለነገ፡ ይዘምታል፤
ዛሬን፡ ተመርኩዞ፣
የሚጋዘውን፡ አግዞ።
በዛሬ፡ ድልድይ፡ ተሻግሮ፣
አገይ፡ ነገዩን፡ ለይቶ፣ ያላጤነነውን፡ ዘክሮ፣
ታሪክ፡ ትንቢትን፡ ይሆናል፤
ጎደመጡቱ፡ መልካም፡ ዋቢነት፡ ይቆማል፤
ለሚዘልቁቱ።
በሚሥቁበት፡ ማና፡ እየሣቀ፡ ይዘልቃል፤
ዕብሪተኞችን፡ ቢሉ፡ ይጨፈልቃል።



## ማሳረጊያ

ከእውነት፡የበለጠ፡ፀጋ
ከነፍስ፡ከሥጋ፡የተቆራኘ፡
የሰውነት፡ዜጋ፡
የለም፡ባይ፡ነኝ፤
አሁንም፡እላለሁ፡ደግሜ፤
ምን፡ቢከፋ፡ምሬቱ፤ ምን፡ቢፀና፡ሕማሜ።

ይሁን!



በግጥሞቹ፡ ውስጥ፡ አንዳንድ፡ ቃላት፡ ለአንባቢ፡ "እንግዳ" ይሆናሉ፡ ብዬ፡ በመገመት፡ አጭር፡ መዝገበ፡ ቃላት፡ ለመፃፍ፡ አስቤ፡ ተውኩት። በአማርኛ፡ ተፅፈው፡ ያሉትን፡ መዝገበ፡ ቃላት፡ አገላብጦ፡ ትርጉማቸውን፡ ማግኘት፡ ይቻላልና። በተለይ፡ ግን፡ "ራእየ፡ ግምበኛ፡ ዘአራዳ፡ ጊዮርጊስ"፡ የሚለው፡ አማርኛውና፡ ግዕዙ፡ "ተዳቅለው"፡ የሚገኙበት፡ ስለሆነ፡ የግጥሙን፡ "ትርጉም"፡ ለመረዳት፡ ፍንጭ፡ ይሆን፡ ዘንድ፡ ግዕዙ፡ እንግዳ፡ ወይም፡ ባእድ፡ ለሆኑባቸው፡ የግዕዙን፡ ቃላት/ሐረጎች፡ ፍቺ፡ ከዚህ፡ በታች፡ አሠፍራለሁ። ግጥሙ፡ ገጽ፡ 29-30 ላይ፡ ነው።

ራእየ፡ ግምበኛ፡ ዘአራዳ፡ ጊዮርጊስ

የአራዳ፡ ጊዮርጊስ፡ ግምበኛ፡ ራእይ

ራእይ = ሕልም፡ (በእንግሊዝኛው፡ vision ወይሚለው ይጠጋል፤ በመጽሐፍ፡ ቅዱስ፡ 'revelation')

ግዘፍ = ሥጋ፣ አካል

ህልውና = ሁነታ፣ ኑሮ፣ እኗኗር

ኅሩያን፡ በህልውናሆሙ = በሁነታቸው፣ በኑሯቸው፡ የተመረጡ፡

ፃድቃን፡ በሕገጋቴሆሙ = በሕጋቸው፡ የፀኑ፤ በውስጠ፡ ወይራ፡ አነጋገር፡ ወይም፡ በመሠሉቅ፡ ዓይነት፡ በሕጋቸው፡ "እውነተኞች፡ የሆኑ" (ሲፈርዱ፡ እንደማ ለት)

ልፀሉፀ፡ ካመ፡ መዳልው፡ በፍትሖሙ = ፍትሕ፡ ሲሰጡ፡ የማያዛቡ፤ ርቱዕ፡ የሆኑ። (ሥነቅ)

ልፀሉፀ = የተባ፣ ትክክል፡ የሆነ፤ ልስልስ፡

መዳልው = ከወርቅ፡ ሚዛን፡ ላይ፡ እንደሰንበታ፡ ወይም፡ ሰዪፍ፡ ሆኖ፡ ቀልቀል፡ የሚወርድ፡ የሚዛኑን፡ ትክክለኛነት፡ የሚያሳይ

ዘኃረዮ፡ አርእስቲሆሙ =(ቃል፡ በቃል) ራሶቻቸው
ን፡ የመረጠው፡ የሾመው፤ በአገባቡ፡
ራሳቸውን፡ የመረጠ

ትፋፋቅ፤ ኃይሬቅ = ምዕዋት፤ ለነፍስ፡ ተሰክሎ፡ ለ
ይሁ፡ የሚሰኝ፡

ለባዊ = ልብ፡ ያለው፤ የሚሰተውል፤ የሚያስብ፡
ነባቢ = አሳብ፡ የሚናገር፡
ገባሪ = ሰሪ፤ ፈጣሪ
(በሃይማኖት፤ የሰው፡ ነፍስ፡ በሦርያት
ለባዊነት፤ ነባቢነት፤ ሕያውነት፡ ናቸው፤
እነዚህ፡ ሕያውነት፡ ገባሪነት፡ በሚለው
ፅንሰ፡ ሐሳብ፡ ተተክቷል)

ሕገ፡ ትፋያን = የምርጦች፡ ሕግ፡

በኣጸጣኑ፡ ጠገባ = በንቂት፡ ጨውር (የበኃይነቶችን፡
የተገዢነትን፡ ጣጣ፡ ይጠቅሰዋል፡)

መለኮት = የአምላክነት፡ ባሕርይ

ሰብእና = ሰውነት — የሰውነት፡ ባሕርይ

ይህ፡ ማንም፡ "ሙከራዊ"፡ ነው፡፡ ሰፋ፡ ባለ፡ አገባቡ፡ እንግሊዝኛው፡ "ኤክስፐርሚንታል"፡ ከሚለው፡ ይመደባል፤ የአማርኛውና፡ የግዕዙ፡ መደባለቅ፡ ለቋንቋ፡ ወይም፡ ለጎን፡ የተደረገ፡ ቢሆን፡ ምክንያት፡ አለው፡፡ የግዕዙ፡ በአማርኛ፡ ተተርጉሞ፡ ቢቀር፡ ክቻውን፡ ሚዛን፡ አያነሣም፡፡ የዳኛ/የምርምር፡ ጣጣ፡ ነው፡፡ በዚህ፡ አገባቡ፡ ቃላት/ሐረጋት፡ እንደ ሰይፍ፡ ሁለት፡ ወገን፡ ስለት፡ አላቸው፡፡